ዓላማ ቢስ ፡ ብኩን ፡ ዘባራቂ ፡ ያዝ ለቀቅ የሚያደርግ ይሆናል። በአንድ ድርሰት ውስጥ ብዙ ፍሬ ነገር ይዞ መነሣት ለአንዱም እንኳ በቂ ትኩረትና ጥልቀት ለመስጠት ሳያመች ይቀራል ።

### ፩·፩ የድርሰት መግቢያ

እንግዲህ አርእስትን ደኅና አድርጎ መረዳትና ዓላማን መወሰን ድርሰት ከመጀመሩ በፊት የሚታሰብባቸው ጉዳዮች መሆናቸው ነው ። አንዳንድ ሰዎች ድርሰት ሲጀመር በቀጥታ ወደ ፍሬ ነገሩ መሔድ ጥሩ መንገድ አይደለም ፡ የድርሰት መግቢያ የግድ ያስፈልጋል ይላሉ ።

የድርሰት መግቢያ የሚያስፈልግበት ጊዜ አለ ። መግ ቢያ የነገር መነሻ ወይም መወሰኛ ማለት ነው ። ብዙውን ጊዜ በመግቢያ ውስጥ የሚጠቀሰው የድርሰቱ ዓላማና ዋና ዋናው ነገር ነው ። ለምሳሌ ስለ ታሪክ ፡ ስለ ሥነ ፍጥረት ፡ ስለ አንድ ዐይነት የጥናት ውጤት የሚጽፍ ሰው ጽሑፉ የሚይዘውን ዋና ዋና ፍሬ ነገር ባጭሩ ቢጠቅስ አንባቢውን በጣም ሊረዳው ይችላል ። ነገር ግን ፡ አንድ ልብ ወለድ ታሪክ የሚጽፍ ደራሲ በዚህ መንገድ ቢሔድ መጽሐፉ በቀላሉ አንባቢ ሊያጣ ይችላል ። ምክንያቱም ልብ ወለድ ታሪክ የሚነበበው በይበልጥ ስለ ታሪኩ ሲባል ስለሆነ ፡ የታሪኩንም ይዞታ እመግቢያው ላይ ባጭሩ አንባቢ ከተረዳ መጽሐፉ ውስጥ ምን ይኖር ይሆን የሚለት ጉጉቱ ስለሚዳከምበት ነው።

ብዙ አስተማሪዎች ድርሰት ሲጽፉ አርእስቱን የሚ ፈታ አጭር ውሳኔ እንደ መግቢያ አድርጎ መነሣት ያስፈል

ጋል የሚል እምነት በተማሪዎቻቸው ላይ ያሳድሩ ይመስላል። ምክንያቱም ተማሪዎች ለማንኛውም አርእስት ውሳኔ ፡ ወይንም ፍች ለመስጠት ስለሚሞክሩ ነው ። እንዲህም ሲያደርጉ ይበልጡን ጊዜ የሚሰጡት ፍች የተዛባና የማያጠግብ ይሆናል ።

እላይ የተነገረው መግቢያ የሚያስፈልግበትና የማያስፈልግበት ጊዜ እንዳለ ፡ እንዲሁም ለአርእስት ፍች መስጠትና አለመስጠትም የሚያስፈልግበት ጊዜ አለ ። ለምሳሌ ፡ አንድ አርእስት የያዘው ሐሳብ ለሰው ፈጽሞ የማይገባ ፡ እንግዳ ሆኖ ከተገኘ አጭር ማብራሪያ መስጠት አንባቢን ይረዳል ። ነገር ግን ፡ ብዙ ተማሪዎች እንደሚያደርጉት የማብራሪያው መንገድ "እንዲህ ማለት እንዲህ ማለት ነው" የሚለው መንገድ ብቻ አለመሆኑን መገንዘብ ያሻል ። እንዲያውም በዚህ መንገድ ብዙዎቹ የሚያቀርቡት ፍች በጣም ደካማና አንዳንድ ጊዜም ፍጹም የተሳሳተ ይሆናል ። ለምሳሌ ፡ አንዱ ስለ መጽሐፍ ለማብራራት ሲፈልግ ፡ "መጽሐፍ ማለት ሰው የሚያነበው የጽሑፍ ክምችት ነው" ብሏል ። ይህ ውሳኔ መጽሐፍ ምን እንደሆነ ለማያውቅ ሰው ምንም አያስረዳም ። መጽሐፍ ምን እንደሆነ ለሚያውቅ ሰውም ቢሆን ከሚያውቀው በላይ የጨመረለት ነገር የለም ። እንዲያውም የጐደለው ነገር ስላለ ሊያደናግረው ይችላል ። ስለዚህ አርእስቱ ጉልህ ፡ ግልጽ የሆነና ለማንኛውም ሰው የማያስቸግር ከሆነ ውሳኔ ለመስጠት በመሞከር ፋንታ በቀጥታ ወደ ፍሬ ነገሩ መሔድ ይሻላል ።

መግቢያ ባስፈለገ ጊዜ ፡ በታቻለ መጠን አንባቢን የሚማርክና ጽሑፉን እንዲያነብ የሚገፋፋው መሆን አለ

በት። ለምሳሌ ፡ አንዳንድ ሰዎች ከድርሰቱ ዋና ዓላማ ጋር የሚስማማ ምሳሌ ከሰው ጽሑፍ ውስጥ አንድ ጥቅስ በማቅ ረብ ይጀምራሉ ። የሆነው ሆኖ ፡ እዚህ ላይ ማስተዋል ያለብን መግቢያው ያለመጠን መርዘም የሌለበት መሆኑን ነው ። አንዳንድ ተማሪዎች አንድ ገጽ የሚሞላ ድርሰት ሲጽፉ ግማሹን ወይንም ከዚያ የሚበልጠውን መግቢያ ያደርጉ ታል። ለምሳሌ ያህል የሚከተለውን ድርሰት እናንብብ ።

ለዐሥራ ሁለተኛ ክፍል መልቀቂያ ፈተና በ1957 ከአንድ ተፈታኝ የቀረበ ድርሰት

## ደሀ አደግ ልጅ

በአንዲት ትንሽ መንደር ቁጥራችን መጠነኛ የሆንን ሰዎች እንኖር ነበር ። በዚያች መንደር እንኖር የነበርነው ሁሉ ጎረቤት እንደ መሆናችን መጠን የመተዛዘን ፡ የመፈቃቀር ፡ የመተባበርና የመከባበር ተግባር በላያችን ላይ ሰፍኖ ፡ በአዕምሮአ ችን ታስቦ በሥራ ላይ አውለነው ነበር ። እንደ ዘመኑና እንደ አገሩ ልማድ የመረዳዳታችን ተግባር በዘርፍ በዘርፍ በየዕለቱ መቀጠሉን አያቋርጥም ነበር ።

በዚያች መንደር እንኖር ከነበርነው ሰዎች መካከል ፍቅራችን ላቅ ያለ ፡ ጠባያችን የተመሳሰለ ፡ በጠቅላላው ከጉርብትና ሌላ የግል ፍቅር የነበረን እኔና አያ ሳያየኝ ነበርን። በኔና ባያ ባያየኝ መካከል የነበረው ፍቅር ፡ ጊዜ የማይሽረው ፡ ዘመን የማይለ ውጠው ፡ ከአንገት ሳይሆን ከአንጀት መሆኑን ሊገልጽልን የሚችለው በጐረቤቶቻችን ዘንድ የሁለ ታችንም የሐሳብ መስማማት በየቀኑ እየቀጠለ መሔዱ ነበር ። አያ ሳያየኝ በነበረበት ዘመን ቤቱ የሞቀ ፡ ትዳሩ የደመቀ ፡ በቤትና በውጭ ያለው ሀብት ለራሱ ቀርቶ ለጐረቤት ተስፋና መመኪያ ነበር ። እግዜር መቼም ሁሉን አሟልቶ ስለማይሰጥ፡ አያ ሳያየኝና ባልተቤቱ የልጅ ጉጉት ሙሉ ደስታቸ ውን ግማሽ በግማሽ ይቀንሰው ነበር ። እንዲያውም አያ ሳያየኝ ባለጸጋ ያደረገውን ፈጣሪውን እንዲህ እያለ የወቀሳ ቃል ይሰነዝርበት ነበር። ምኑን ሀብት ሰጠኸኝ ፡ ከዚህ ሁሉ ሀብት ይልቅ አንድ ፋንጋ ልጅ ብትሰጠኝ እያለ ያማርረው ነበር ። ነገር ግን እግዚአብሔር ለቸርነቱ አይቆጣጠሩትምና አያ ሳያ የኝ ከሚወዳት ሚስቱ አንድ ወንድ ወለደ ።

አያ ሳያየኝ በብዙ ልመና የወለደውን ልጁን ሳያሳድግ እሱና ባልተቤቱ በድንገት በተስቦ በሽታ ሞቱ ። በዚህ ጊዜ በስለትና በልመና የተወለደው ሕፃን ዕጓለ ማውታ ሆነ ። የናትና የአባቱን ሀብት ዘመድ አዝማድ ስለ ተከፋፈለው ሕፃኑ ለማደግ

የገጠመው የኑሮ ችግር በጣም ያንገፈግፍ ነበር። ለነፍሴ ያለ ለሕይወቱ መጠገኛ ያህል ይለግስለት ነበር። ይሁን እንጂ ፡ ይህ ልጅ ደሃ አደግ በመሆኑ ስውነቱ እየመነመነ አቅሙ እየደከመ መሔዱ አልቀረም ። አያ ሳያየኝ በሕይወት በነበረበት ጊዜ የነበረንን ፍቅር በማስታወስ ይኽን ደሃ አደግ ልጅ ዘመን በተበላሸ ጊዜ ከመንግሥት ትምህርት ቤት ከድሆች ማሳደጊያ በማስገባት የዘመኑን ዕውቀት እንዲገበይ አደረኩት ። ስለዚህ ደሃ አደግ ልጅ የዘመኑን ዕውቀት ለመሳተፍ በቃ ።

ይህን ድርሰት የጻፈው ተፈታኝ ፡ በማያስፈልገው ንዑስ ሐሳብ ላይ ከሚገባ በላይ አጉል መራቀቁን ማስተዋል ይቻላል ።

ለምሳሌ ፡ “በኔና ባያ ሳያየኝ መካከል የነበረው ፍቅር ፡ ጊዜ የማይሽረው ፡ ዘመን የማይለውጠው ፡ ካንገት ሳይሆን ከአንጀት መሆኑን ሊገልጽልን የሚችለው በጐረቤቶቻችን ዘንድ የሁለታችን የሐሳብ መስማማት በየቀኑ እየቀጠለ መሔዱ ነበር” በሚለው ዐረፍተ ነገር ውስጥ “በጐረቤቶቻችን ዘንድ የሁለታችን የሐሳብ መስማማት በየቀኑ እየቀጠለ መሔዱ ነበር” ሲል አንደኛ ሐሳቡ ግልጽ አይደለም ። ሁለተኛም ዐረፍተ ነገሩ በጠቅላላው ለድርሰቱ አርእስት ምንም አያስፈልግም ። ጸሐፊውን ከዐላማው እንዲወጣ አድርጎታል ። ምክንያቱም የርሱና ያያ ሳያየኝ መግባባት ጨርሶ ከአርእስቱ ውጭ ነው ። ይህ ዐረፍተ ነገር ለምሳሌ ያህል ተጠቀሰ እንጂ ሐተታው በጠቅላላው ዓላማውን

ስቷል ለማለት ይቻላል ። ሆነም ቀረም ስለ "ዶሃ አደግ" ልጅ በቀጥታም ሆነ በተዘዋዋሪ መንገድ ጥቂት የተጠቀሰ ነገር ቢኖር በመጨረሻው አንቀጽ ውስጥ ብቻ ነው ። ስለዚህ እንዲህ ያለው ድርሰት በመግቢያ ላይ የማያስፈልግ ረጅም ሐተታ ለሚያቀርቡት ተማሪዎች ጥሩ ምሳሌ ነው ።

## ፮.2 አንቀጽ

ከዚህ በላይ የድርሰትን አርእስት ዶጎና አድርጎ ስለ መረዳት ፡ ዓላማን ስለ መወሰንና ስለ መግቢያ ተነጋግረናል ። ቀጥለን ድርሰትን በአንቀጽ ስለ መከፋፈል ፡ እንነጋገር ።

የድርሰታችንን ዓላማ ከወሰን በኋላ ፡ ዓላማውን ለማጉላት ልዩ ልዩ ሐሳቦች እናቀርባለን ። እነዚህም ልዩ ልዩ ሐሳቦች ራሳቸውን የቻሉ አንዳንድ የድርሰት ክፍል ናቸው ። እንደነዚህ ያሉትን አንቀጾች እንላቸዋለን ። በሌላ አነጋገር አንድ አንቀጽ አንድ ራሱን የቻለ አጭር ድርሰት ነው ሊባል ይቻላል ። እያንዳንዱም አንቀጽ ሲጻፍ በአዲስ መሥመር ትንሽ ወደ ቀኝ ገባ ተብሎ ነው ። ይህም ዘዴ አንባቢ በድርሰቱ ውስጥ ያለውን እያንዳንዱን ንዑስ ሐሳብ በቀላሉ እንዲገነዘብ ለማድረግ ይጠቅማል ። ብዙ ንዑስ ሐሳቦች በአንቀጽ ሳይከፋፈሉ መደዳውን ተጨናንቀው ሲቀርቡ የመጀመሪያው ሐሳብ የት ላይ አብቅቶ ሁለተኛው ወይንም ሦስተኛው የት እንደ ጀመረ ለመገንዘብ እጅግ ያዳግታል ።

ለምሳሌ ፡ የምንጽፍበት የድርሰት አርእስት "አንድ ደራሲ በቃላት አመራረጥ ረገድ የሚያደርገው ጥንቃቄ" የሚል ይሁን ። ለዚህም አርዕስት የሚስማሙ ልዩ ልዩ አንቀጾች ለማውጣት የፈለግን እንደሆነ ፡ አንደኛው አንቀጽ

ደራሲው ቃላቱን በተለመደ ፍቻቸው እንደፈት እንደሚሠራበ

ቸው ሊያብራራ ይችላል ። ሁለተኛው አንቀጽ ከአንድ በላይ ፍች ያለው እያንዳንዱ ቃል ወይንም ሐረግ ደራሲው ራሱ በፈለገው መንገድ ብቻ መግባቱ ሊታተትበት ሲችል ፡ የውጭ ቋንቋ አለመቀየጡም የሦስተኛው አንቀጽ ይዘት ሊሆን ይችላል ። በዚህ ሁናቴ በመከፋፈል ብዙ አንቀጽ ይጻፋል ።

እያንዳንዱንም አንቀጽ ጥሩ አድርጐ ለመጻፍ የሚረዳን መንገድ ፡ በድርሰቱ ውስጥ ልናስገባቸው የፈለግናቸውን ሐሳቦች ከለየን በኋላ ለያንዳንዱ አንድ አጠቃላይ ወይንም መንደርደሪያ ዐረፍተ ነገር መጻፍ ነው ። ከዚያ በኋላ ፡ ይህን ዐረፍተ ነገር የሚያብራሩ ወይንም ለሱ ምሳሌዎች የሚሆኑ ዐረፍተ ነገሮች በቅደም ተከተል ይሰፍራሉ ። ለምሳሌ ፡ የድርሰቱ አርእስት ቅድም የጠቀስነው "አንድ ደራሲ በቃ ላት አመራረጥ ረገድ የሚያደርገው ጥንቃቄ" ቢሆን ፡ አንዱ አንቀጽ የሚከተለው ሆኖ መንደርደሪያው የመጀመሪያው ዐረፍተ ነገር ሊሆን ይችላል ።

ታደሰ የተባለው ደራሲ በድርሰቱ ውስጥ ቃላትን በተለመደ ፍቻቸው ያስገባል ። ለምሳሌ አንዳንድ ሰዎች "መናኛ" የሚለውን ቃል እርካሽ በሚል ትርጉም ያገቡታል። በታደሰ ጽሑፍ ውስጥ ግን እንዲህ ያለውን ስሕተት ፈልጎ ማግኘት ፈጽሞ አይቻልም ። እንዲሁም አንዳንድ ሰዎች "ወሰደ" የሚለውን ቃል ባልተለመደ መንገድ "ቡና ወሰደ ፡ ምግብ ወሰደ" ሲሉ ታደሰ ግን ፡ ይህን ዐይነት አነጋገር አጥብቆ ይቃወማል ። በዚህ ቃል ምን ለማለት ፈልጎ ይሆን የሚል ዐይነት ጥያቄ በአንባቢው አዕምሮ ውስጥ እንዲነሣ አይፈልግም ። ባጭሩ ታደሰ በሚጽፈው ሁሉ ቃላት በተለመደው ፍቻቸው መሠረት እንዲገቡና አንባቢንም እንዳያደናግሩ ለማድረግ አጥብቆ ይጥራል።

የሚከተሉትም ሁለት አንቀጾች ለጥሩ አንቀጽ አሠራር ተጨማሪ ምሳሌዎች ናቸው ፡

ሀ/ ለመጀመሪያ ጊዜ በኩራት ዐይን የቤቱን ዕቃ አንድ ባንድ ይመለከት ገባ ። ውጭ የደመቀ የፀሐይ ብርሃን ቢኖርም ፡ የዝምታው አዘቅትና ጽላሎት በስውር መንገድ ተዋህደው የእንግዳ ቤቱን ብርሃን ደበብ አድርገውታል ። በብርሃን ዐይን የሚያሞቀው የምንጣፉና የሶፋዎች ደማቅ ቀይ ቀለም አሁን የረጋ ደም መስሏል ። ወርቅማ ሆነው በጥቁር ጥለት

ያጌጡት የመስኮት መጋረጃዎች በብርሃን ያላቸውን ድምቀት አጥተው ፈዝዘዋል ። ከውጭ ወደ ውስጥ ሲገቡ በስተቀኝ ካለው ግድግዳ ላይ የተሰቀለው በኅብረ ቀለማት ስለ ቀለማት የተሠራው ሥዕል ብርሃን በማጣቱ የቅኔው ውበት ጠፍቷል [4]

ለ/ ፊታውራሪ መሸሻ ሳይሸመግሉ ከሰው ጋር ተጣልተው ካልተከሰሱ እሳቸው ከሰው በዘመድ ይሁን በአካል ዳኛ ፊት ቆመው አየሁዋቸው የሚል ሰው አልነበረም ። ብዙ ጊዜ ከሰው አይጣሉም ፣ ከተጣሉ ግን እከሳለሁ ከማለት እፋለማለሁ ማለት ይቀናቸዋል። "ለዳኛ አቤት ማለት ደካማነትን ወይንም ፈሪነትን አምኖ እርዳታ መለመን ነው" ይሉ ነበር ። ተመትቶ ወይንም ተሰድቦ ካሱኝ ከሚል መትቶ ወይም ሰድቦ ካሳ የሚከሰውን የሚያከብሩ መሆናቸው በማንም ዘንድ የታወቀላቸው ነበሩ ። አገረ ገዥ ሆነው በዳኝነት ወንበር ይቀመጡ በነበር ጊዜ እንኳ ተመትቶ ላቤቱታ የመጣባቸውን "እጅ የለህም ወይ?" ተሰድቦ የመጣባቸውን "አፍ የለህም ወይ" ይላሉ... [5]

በአንቀጽ ሀ. ውስጥ የመጀመሪያው ዐረፍተ ነገር መንደርደሪያው ፀረፍተ ነገር ሲሆን ፣ የቀሩት ዐረፍተ ነገሮች ይህንኑ የሚያብራሩ ናቸው ።

በአንቀጽ ለ. ውስጥ መንደርደሪያው ሦስተኛው ዐረ

---

4 በዓሉ ግርማ ፣ ከአድማስ ባሻገር ፣ አርቲስቲክ ማተሚያ ቤት ሦስተኛ እትም ፣ 1967 ገጽ 7

5 ሐዲስ ዓለማየሁ ፣ ፍቅር እስከ መቃብር ፣ ብርሃንና ሰላም ማተሚያ ቤት ስድስተኛ እትም ፣ 1977 ፣ ገጽ 465

ፍተ ነገር ነው ። በዚህም መንደርደሪያው ዐረፍተ ነገር ሁልጊዜ የአንቀጹ መጀመሪያ ዐረፍተ ነገር መሆን እንደሌለበት ማስተዋል ያሻል ። ምናልባት ላንዳንድ አንባቢ የመጀመሪያው ዐረፍተ ነገር መንደርደሪያ ሊመስል ይችል ይሆናል ። ይህ ዐረፍተ ነገር ግን ፣ በሦስተኛው ዐረፍተ ነገር ውስጥ ያለውን ሐሳብ የሚያጐላ ነው ። የሚገልጸውም ባጭሩ ፊታውራሪ መሸሻ በከሳሽነት እዳኛ ፊት አለመቅረባቸውን ብቻ ነው ። ምክንያቱን አይጠቁምም ። ሌሎች ሰዎች ከሳሽ ሆነው ለዳኝነት ሲቀርቡ ለምን ቅር ይሰኙ እንደ ነበርም ፍንጭ አይሰጥም ። ሦስተኛው ዐረፍተ ነገር ግን ለሁሉም ምክንያት ሆኖ ቀርቧል ። ስለዚህ የአንቀጹን ፍሬ ሐሳብ የሚያጠቃልለው እሱው ነው ።

በየንዳንዱ አንቀጽ ውስጥ ያሉት ዐረፍተ ነገሮች እርስ በርሳቸው መዛመድ እንዳለባቸው ሁሉ ፣ በአንድ ድርሰት ውስጥ የሚገኙ አንቀጾችም እርስ በርሳቸው በሐሳብ ሰንሰለት የተያያዙ መሆን አለባቸው ። ባጭሩ በአርእስቱ የተጠቀሰው ሐሳብ ወይንም የድርሰቱ ዋና ዓላማ በልዩ ልዩ መልኩ በየንዳንዱ አንቀጽ መገኘት አለበት ። ይህን መንፈስ ያልያዘ አንቀጽ በድርሰት ውስጥ ቢገኝ ከዓላማው ወይንም ከአርእስቱ የወጣ አንቀጽ ነው ይባላል ።

ድርሰቱ ወደ መጨረሻ ሲደርስ ተገቢ ወደ ሆነ ፍጻሜ መድረሱ ለአንባቢ ሊሰማው ይገባል ። ከብዙ ተማሪዎች ድርሰት ጉድለት አንዱ ፣ ሐሳብ ሲያልቅ በድንገት ማቋረጡ ነው ። ሐሳቡ ወደ አንድ ፍጻሜ መድረሱ ለአንባቢው በሚገባ ካልተሰማ “ድርሰቱን እዚህ ላይ አቆማለሁ ፣ እገታለሁ ፣ አበቃለሁ ፣ እፈጽማለሁ” የሚለው ዐይነት የመጨረሻ

ዐረፍተ ነገር ለድርሰቱ መደምደሚያ ሊሆን አይችልም ። ብዙዎች ተማሪዎች ግን ፣ ሐሳባቸው ሲያልቅባቸው ድርሰቶቻቸውን የሚዘጉት በዚህ መንገድ ነው ። መግቢያ አስፈላጊ በሆነ ጊዜ የድርሰቱ ዋና ዓላማ ምን እንደሆነ ባጭሩ የሚገለጽበት ክፍል እንደ መሆኑ ፣ መደምደሚያም አብዛኛውን ጊዜ በድርሰቱ ውስጥ ምን ምን እንደ ተገለጸ ባጠቃላይ መንገድ የሚቀርብበት ክፍል ነው ።

ለምሳሌ የሚከተለውን እንመልከት ።

## ዲሞስቴን

በዛሬው ሥልጣኔ የመንግሥት መሪዎች የሚሆኑ ሰዎች የመንግሥት መማክርት በሚገኙበት ጉባኤ ወይም ሕዝብ በተሰበሰበበት ሸንጎ አንደበት ርቱዕ በመሆን የሰሚዎቻቸውን መንፈስ በንግግራቸው እየቀሰቀሱ ልባቸውን መማረክ የሚችሉበት ሶጦታና ችሎታ ያላቸው ሰዎች ሆነው መገኘት አስፈላጊ ሆኖባቸው ሲጣጣሩበት እንመለከታለን ። ከዚህም የተነሣ ንግግር የማወቅ ሙያ በዲሞክራሲ አገሮች እንቸርችልን በዲክታተር አገሮች ሂትለርና ሙሶሊኒን ለመሰሉ ሰዎች ሥራቸውን የተቃና ለማድረግና ሥልጣናቸውን ለማጠናከር በጣም የሚጠቅም ትልቅ መሣሪያ ሆኖ አገልግሏል ። የሆነ ሆኖ ፣ ይህን ጥበብ ወደ ማሰተዋል እንመለስና የንግግር (ዲስኩር) ሙያና የዲሞስቴን ስም የተባበሩ መሆናቸውን እናስተውል ።

የንግግር ዐዋቂ በመሆኑ ይመሰገን የነበረው

ካሊስትራት የሚባለው ሰው ሲናገር ለመስማት አስ በው ፡ አንድ ቀን የዲሞስቴን አስተማሪዎች ወደ ሸንጎ ሲሔዱ ዲሞስቴንም ከነሱ ጋር አብሮ እንዲሰማ ይዘውት ሔዱ ። ዲሞስቴን የዚህን ሰው ንግግር በመስማትና በሸንጎው ላይ በነበሩትም ሰዎች ዘንድ ምን ያህል እንደ ተደነቀ በማስተዋል ብርቱ ስሜት በመንፈሱ አድሮበት ልቡ ወደዚህ ጥበብ የተሳበው ከዚያ ቀን ጀምሮ ነው ብለው የሚናገሩ ሰዎች አሉ ።

ዲሞስቴን በመጀመሪያ ከጉባኤ ላይ ቀርቦ በተናገረ ጊዜ ንግግር የማይችል ሆኖ ስለ ተገመተ ንግግሩን እያቋረ ጡበት ሁለት ጊዜ መለሱት ። ይህም የሆነበት ምክንያት ድምፁ ደካማ ፡ ምላሱ ኮልታፋ ፡ ትንፋሹ አጭር ስለ ነበረ ንግግሩ እየተሰባበረበት በሰሚዎቹ ዘንድ ሊደመጥ የማይገባው ሆኖ በመገኘቱ ነው ። የባለቅኔዎች ፡ የፈላስፎች ፡ የሊቃውንት ፡ የደራሲያን አገር በመሆኗ ለማንኛውም ሰው ቢሆን በአቴና ሕዝብ ዘንድ ቀርቦ ዲሞስቴን በነበረበት ዘመን በጉባኤ ፊት ለመናገርና ተሰሚነትን ለማግኘት በዚሁም ደግሞ ለመመስገን በውነቱ ቀላል ነገር እንዳልነበረ መዘንጋት አይገባም ።

ከዚያ በኋላ ፡ ዲሞስቴን ከሰው ተለይቶ እንደ ባሕታዊ ብቻውን እየኖረ ንግግር የማሳመርን ጥበብ ይማር ጀመር ። የሚንተባተበውን ምላሱን ለማፍታ ታት ሲል ባፉ ውስጥ ጠጠር እየጨመረ ብቻውን ሆኖ እንደ እብድ ሰው ከፍ ባለ ድምፅ በመናገር አንደበቱን ገራው ። እንደዚሁም ደግሞ ፡ በጉባኤ ላይ ቀርቦ

በሚናገርበት ሰዓት ሕዝብ ንግግሩን ለማቋረጥ የሚያደርግበትን የታቃዋሚነት ውካታ ለመልመድና ለማሸነፍ እንዲረዳው ሲል ከባሕር ዳር ቆሞ ጮኾ በመናገር የባሕሩን ውሃ ማዕበል ሲመታው ከሚያደርገው ጩኸት ጋር ንግግሩን ያወዳድር ነበር ። በመሬት ውስጥ የሚኖርበትም ዋሻ አዘጋጅቶ ብዙ ወራት ሙሉ ከዚያ ሳይወጣ ሰው አሳቡን በምልካም ንግግር የሚገልጥበትን ዘዴ ሲሻ ቱሲዲድ የሚባለው ሊቅ የጻፈውን መጽሐፍ እየደጋገመ እስከ ስምንት ጊዜ ድረስ ይገለብጥ ነበር ። ከተደበቀበትም ጉድጓድ ውስጥ ወጥቶ ሕዝብ ወደሚገኝበት ቦታ የመሔድ ሐሳብ በመንፈሱ ውስጥ እንዳይገባ ለማድረግ ሲል የራሱን ጠጉር ግማሹን ተላጭቶ ግማሹን ትቶ ከሰው ዘንድ ሊቀርብ የማይችል አስቀያሚ መልክ ይዞ ኖረ ።

ይህን በመሰለ አኳኋን ብቻውን እየኖረ ራሱን ለራሱ መምህር አድርጎ በማሰብ ፡ በመመራመር ፡ ቃሉን ከፍ አድርጎ ብቻውን በመናገር ፡ በመጻፍና በመግልበጥም ስምንት ዓመት ሙሉ መንፈሱን እያበለጸገ እንደቢቱን ካረመና ምላሱን ከሳለ በኋላ ፡ ዲሞስቴን እንደ ገና ከጉባኤ ፊት ቀርቦ ተናገረ ። በዚህ ጊዜ ግን ፡ የተሰበሰቡት ሰዎች ሁሉ ንግግሩን ሲሰሙ እጅግ አድርገው ተደነቁ ፡ ዲሞስቴንም አስቦት ከነበረው ዐላማ ደረሰ ።[6]

6 ከበደ ሚካኤል "ታላላቅ ሰዎች" አርቲስቲክ ማተሚያ ቤት ፡ ሦስተኛ እትም ፡ 1956 ፡ ገጽ 45 46 (ለተፈለገው ዓላማ እንዲስማማ መጠነኛ ለውጥ ተደርጎበታል)

ከዚህ በላይ ያለው ምንባብ ለአንድ ሙሉ ድርሰት አጠር ያለ ምሳሌ ሊሆን ይችላል ። የመጀመሪያው አንቀጽ የድርሰቱን ይዘት አዝማሚያ ስለሚጠቁም እንደ መግቢያ ይቆጠራል ። በዚሁ አንቀጽ የመጨረሻው ዐረፍተ ነገር ወደሚቀጥለው አንቀጽ እንድናመራ ያደርገናል ። የዚህ ዐይነቱ ዐረፍተ ነገር መሸጋገሪያ ዐረፍተ ነገር ይባላል ።

ከዚያም የሚከተሉት ሦስቱ አንቀጾች የድርሰቱ ዋና አካል ሲሆኑ ፡ የመጨረሻው አምስተኛው ግን መደምደሚያ ነው ።

## 6·3 የሐሳብ አቀራረብ

ከዚህ በፊት አንድ ሰው ድርሰት ለመጻፍ በሚያቅድ በት ጊዜ የድርሰቱን ዓላማ ወስኖ መነሣት አለበት ብለናል ። ዓላማውንም ለማብራራት የሚያቀርባቸው ማስረጃዎች ሁሉ እርስ በርሳቸው እንደ ሰንሰለት የተያያዙ መሆን አለባቸው ። የሚቀርበውም ሐሳብ ሁሉ ለዚያ ለተገኘበት ቦታ ተስማሚ ሆኖ መገኘት አለበት ፡ እንዲህም ማለት ማናቸውም ዐረፍተ ነገር ቀዳሚውንና ተከታዩን ሐሳብ የሚያገናኝ ፡ መሰናክል የሌለበት ድልድይ መሆን ይኖርበታል ማለት ነው ። ባጭሩ አንድ አስተዋይ አንባቢ ድርሰቱን በሚያነብበት ጊዜ ‘ይህ ን እዚህ ምን አመጣው? የተነሣበትን ለምን ለቀቀ? ለምን አንዱን ያዝ አንዱን ለቀቅ ያደርጋል?’ የሚል ስሜት እንዳያድ ርበት መጠንቀቅ ያስፈልጋል ።

ከዚህም ሌላ ለሚቀርበው ሐሳብ ሁሉ በቂ ማስረጃ መስጠት ያሻል ። ያለበቂ ማስረጃ በግል ስሜት ተመርቶ እንዲህ መሆን አለበት ፡ መሆን ይገባዋል ፡ ማድረግ ያስፈልጋል ፡ ነው ፡ የሚል ዐይነት አጠቃላይ ውሳኔ ወይንም

ፍርድ መስጠት የጸሐፊውን ደካማነት አጉልቶ የሚያሳይ አጉል ድፍረት መሆኑን መገንዘብ ይገባል ። በተረጋገጠ ሁናቴ ያልታወቀን ነገር ለመግለጽ ባስፈለገ ጊዜ ሊሆን ይችላል ፡ ይመስላል ፡ ሳይሆን አይቀርም ምናልባት በሚል በማመልከት በጉዳዩ በቂ ማስረጃ አለመገኘቱን ወይንም ጥናት የሚያስፈልገው መሆኑን መጠቆም ጠንቃቃ እንጂ አላዋቂ አያሰኝም ።

ምሳሌ ፡ የተወለደው በቤገምድር ክፍለ ሀገር ነው ፡

ስለዚህ የተጣራ አማርኛ እንደሚናገር አያጠራጥርም ።

በዚህ ምሳሌ ውስጥ የተገለጸው ሐሳብ ከአስተዋይ ሰው አንደበት ሊወጣ አይችልም ። ምክንያቱም በቤጌምድር ተወልዶና አድጎ የተጣራ አማርኛ የማይናገር ብዙ ሰው ሊገኝ ስለሚችል ነው ። ከዚሁም በላይ አንድ ሰው በበጌምድር ተወልዶ አማርኛ በማይነገርበት አገር ሊያድግ ስለሚችል ፡ አማርኛው የተጣራ ላይሆን ይችላል ። ደግሞም የተጣራ "አማርኛ" የሚለው ሐረግ የያዘው ሐሳብ ምን እንደሆነ ግልጽ አይደለም ። በንግግሩ ውስጥ የውጭ አገር ቃላት አይቀላቅልም ማለት ነው? የሰዋስው ስሕተት አያደርግም ማለት ነው? የቤገምድር አማርኛ በሌላው ቦታ ከሚነገረው አማርኛ ይበልጣል ማለት ነው? ሐሳቡ ጉልህ አይደለም ። በጠቅላላው በቤገምድር መወለድ አማርኛን አጣርቶ ለማወቅ በቂ ምክንያት ስላልሆነ ፡ የተጠቀሰው ምሳሌ የአስተሳሰብ ጉድለት አለበት ።

ያስተሳሰብ ጉድለት ያለባቸው የሚከተሉት ዐረፍተ ነገሮች ከዐሥራ ሁለተኛ ክፍል ተማሪዎች ድርሰት ውስጥ የተቀዱ ናቸው ።

1/ ኢትዮጵያ ከአፍሪቃ ቀንድ ብትሆንም በእርሻ በኩል ስለ ገበሬዎችና ድብልቅ ከብት አርቢዎች ለምታደርገው ቁጥጥር በቂ ሠራተኞች አላሰማራችም ።

ኢትዮጵያ የአፍሪቃ ቀንድ መሆኗና በእርሻና በከብት እርባታ በኩል በቂ ሠራተኛ አለማሰማራቷ ምን ግንኙነት አላቸው?

2/ ኢትዮጵያ በቡና አምራችነቷ የታወቀች አገር በመሆኗ አብዛኛውን ጊዜ ጥሩ የቡና ዐይነት የሚገኘው ከወለጋ ጠቅላይ ግዛት ነው ።

የወለጋ ቡና በዐይነቱ ጥሩ የሆነው ኢትዮጵያ ቡና አምራች አገር በመሆኗ ነው? ስለዚህ በሁለቱ ሐሳቦች መካከል ማለትም የኢትዮጵያ ቡና አምራችነትና የወለጋ ቡና በዐይነቱ ጥሩ በመሆኑ መካከል ሊኖር የሚገባ መሸጋገሪያ ሐሳብ ጐድሏል ።

3/ የዘመኑ ወጣት ኩሩ ስለሆነ ጊዜውን የሚያሳልፈው በልዩ ልዩ ቦታዎች ላይ ነው ።

የዘመኑ ወጣት ኩሩ መሆንና ጊዜውን በልዩ ልዩ ቦታዎች ላይ ማሳለፉ ምን ግንኙነት አላቸው? ልዩ ልዩ ቦታስ ማለት ምን ማለት ነው?

4/ ምንም እንኳ ከናቴ ማሕፀን ስወጣ የመረረ ልቅሶ ባለቅስም፣ በዚች ዓለም በመፈጠሬ በጣም እደሰታለሁ ። መፈጠሬን ጠላሁ የሚሉት አነጋገር በፍጹም አይገባኝም። ምክንያቱም በመፈጠሬ ቢያስደስትም ፡ ባያስደስትም ብዙ ነገር ስላየሁ ነው ።

በዚህ ምሳሌ ውስጥ ያልተያያዙ ሐሳቦች አሉ ። መጀመሪያ ከናት ማሕፀን ሲወጡ የመረረ ልቅሶ

በማልቀስና በዚች ዓለም በመፈጠር መደሰት በሚለው ሐሳብ መካከል ምንም ግንኙነት የለም ። ሁለተኛ ሰውዬው በመፈጠሩ ብዙ ነገር ማየቱ "መፈጠሬን ጠላሁ" የሚሉትን ሰዎች ሐሳብ ሊያፈርሰው አይችልም ።

5/ ሥነ ጽሑፍ የቃላት አገባብን ፡ ሥርዓተ ነጥብን ፡ ያረፍተ ነገር አስካክን እንደዚሁም የሰዋስውን ደምብ አጠቃሎ የሚይገዝ ነው ። ይሁንና የኢትዮጵያ ሥነ ጽሑፍ መጀመሪያ የተመሠረተው በዕግዝ ላይ ነው ።

ስለሥነ ጽሑፍ የተሰጠው ውሳኔና የኢትዮጵያ ሥነ ጽሑፍ በግዕዝ ላይ መመሥረት ምን ዝምድና አላቸው? የፊተኛውስ ሐሳብ የኋላኛውን ሊያፈርሰው ይቻላል ወይ?

ከዚህ ቀጥለን አንዱን ሐሳብ ጀምሮ በቂ ማብራሪያ ሳይሰጠው ወደ ሌላ ሐሳብ የሚሻገር ወይንም ያገዘ ለቀቅ የሚያደርግ ከአንድ መጽሐፍ የተገኘ ሐተታ ባጭሩ እንጠቅሳለን ።

አሁን በተቻለኝ መጠን ለኢትዮጵያ ልጆች ስለግዕዝ መድከሜ ጉዳታቸውን ለመግለጽ ነው ። የኢትዮጵያ ልጆች ሆይ ዛሬ በአንዳንድ ወንድሞቻችሁ ዘንድ በሚታየው የብስጭት ሥራ በጣም አዝናለሁ ፡ የኢትዮጵያ ምድር ልጆች ትንሽ ብስጭት ባለመቻል ሕይወትን እስከ ማጥፋት መድረሳቸው የሚገርም ነው ። እናታችሁ የኢትዮጵያ መሬት በማሕፀኗ የያዘችውን ባለማወቃችሁ ነው እንጂ ፡ ዐውቃችሁ ቢሆን እንኳንስ ልትሞቱና ልትታመሙ ባልቻላችሁም ነበር ።

ወገኖቼ ሆይ መማር ማለት አስቀድሞ የናት አገርን ቋንቋ ጠንቅቆ ማወቅ ነበር ። እናንተ ግን ፡ አስቀድማችሁ ሁላችሁ የሹመትን ቦታ በመፈለግ የሀገራችሁን ቋንቋ አንማርም በማለት ከባዕድ አስተማሪ ጋር ተባብራችሁ ተዋችሁት ...

እላይ በተጠቀሰው ጽሑፍ ግልጽ ያልሆኑና ያልተዛመዱ ሐሳቦች ተደርድረዋል ። በመጀመሪያ "ስለ ግዕዙ መድከሜ ጉዳታችሁን ለመግለጽ ነው" ሲል የነማንን ወይንም የምኖቹን ጉዳት የሚል ጥያቄ ይነሣል ። ይህ ጥያቄ ሳይመለስ አንዳንድ ኢትዮጵያውያን ወጣቶች በትንሽ ብስጭት ሕይወታቸውን ስለ ማጥፋታቸው ተጠቅሷል ። ይህም ሲሆን የግዕዙ ጉዳይ ተረሳ ማለት ነው ። ከዚያም ቀጥሎ ኢትዮጵያ በማሕፀኗ የያዘችው ቢታወቅ ኖሮ እንኳንስ መሞት መታመምም አይቻልም የሚል ሐሳብ ተሰንዝሯል ። በኢትዮጵያ መሬት ውስጥ ሀብት መኖሩን ማወቅ እንዴት ከመሞትና ከመታመም እንደሚያድን አልተገለጸም ። ይህንን ይተውና "መማር ማለት አስቀድሞ የናት አገርን ቋንቋ ጠንቅቆ ማወቅ" መሆኑን ጠቆም ያደርጋል ። ከዚያም "የሹመትን ቦታ በመፈለግ ያገራችሁን ቋንቋ አንማርም በማለት" ... እያለ ሁለት ግንኙነት የሌላቸው ሐሳቦች አንዱን ላንዱ ምክንያት በማድረግ አቅርቧል ።

### ·4 <u>የድርሰት ዐይነቶች</u>

የተለመዱት የድርሰት ዐይነቶች አራት ናቸው ። እነዚህም ተራኪ ፡ ሥዕላዊ ፡ አመዛዛኝና ገላጭ በሚል ሥያሜ

ይጠራሉ።

6·4·1 ተራኪ

ተራኪ የሚባል የድርሰት ዓይነት ፡ ስላለፈ ድርጊት የሚተርክ ወይንም የሚያትት ጽሑፍ ነው ። ለምሳሌ ፡ ስለአንድ ሰው የሕይወት ታሪክ ፡ ስለአንድ ጦርነት አነሣሥና ፍጻሜ ፡ በአንድ ጉባዔ ላይ ስለ ተደረገ ውይይት ፡ በጠቅላላ ውም ባለፈ ጊዜ የተፈጸመ ነገር እንዴት እንደ ተፈጸመ የሚተርክ ጽሑፍ ሁሉ ተራኪ ድርሰት ይባላል ። የሚከተለው አጭር ምንባብ ለተራኪ ድርሰት አስረጅነት የቀረበ ጽሑፍ ነው ።

አጤ ሚኒልክ 13 ነሐሴ 1835 ዓመተ ምሕረት ባበሻ ቁጥር ባንኮበር ከተማ ከሸዋው ንጉሥ ኃይለ መለኮትና ከወይዘሮ እጅግአየሁ ተወለዱ ።

ካጤ ተክለ ጊዮርጊስ ፍጻሜ መንግሥት ጀምሮ አጤ ምኒልክ ተወልደው ያሥራ ሁለት ዓመት ልጅ እስኪሆኑ ድረስ አገራቸው ሸዋ ባለባቶቹን እያሠለ ጠነ ከቀሩት የኢትዮጵያ አውራጆች ተለይቶ ለብ ቻው መንግሥት አቁሞ ነበር ።

በ1847 ዓ.ም. ንጉሥ ኃይለ መለኮት ሙተው ትልቅ ጦርነት ሳይሆን አጤ ቴዎድሮስ አገሩን ወደ መንግሥታቸው ጨመሩት ። አጤ ምኒልክም ከብዙ ዎች መኳንንት ጋር ተማርከው ወደ በጌምድር መጡ። የሀያ ዓመት ጎበዝ ሆነው ከድተው ወዳገራ ቸው እስኪመለሱ ድረስም ፡ ባጤ ቴዎድሮስ ቤተ መንግሥት በክብር አደጉ ። አጤ ቴዎድሮስ ከሞ ቱም በኋላ መንግሥት ሊይዙ ጣሩ ፡ እንደማይሆንላ

ቸው አይተው ግን ላጤ ዮሐንስ ታጠቁ ። አጤ ዮሐንስም በመጋቢት 1880 ዓ.ም. በመተማ ጦርነት ከሞቱ በኋላ ፡ ለሸዋው ባላባት ወደረኛ የሚሆን ሰው አልተገኘም ። በዚህም ምክንያት በ27 መስከረም 1881 ዓ.ም. አጤ ምኒልክ የንጉሠ ነገሥትን ዘውድ በንጦጦ በእመቤታችን ቤተ ክርስቲያን ጫኑ ።

ይህ ምንባብ የተቀዳው "አጤ ምኒልክና ኢትዮጵያ" ከሚለው ከነጋድራስ ገብረ ሕይወት ባይከዳኝ ድርሰት ውስጥ ነው ። ለተራኪ ድርሰት ምሳሌ ሆኖ የቀረበውም ዐፄ ምኒልክ መቼ እንደ ተወለዱ እንዴት እንዳደጉ ፡ ምን ምን ፈጽመው ለንጉሠ ነገሥትነት እንደበቁ ስለሚተርክ ነው ። ተራኪ ድርሰት ከሁሉም የድርሰት ዐይነቶች ቀለል ያለ ስለሆነ ለምሳሌ ያህል ይህ የተጠቀሰው ይበቃናል ።

6·4·2 <u>ሥዕላዊ</u>

ሥዕላዊ ድርሰት የሚባለው ያንድን ነገር ሁናቴ በዐይን እንዳዩት ፡ በእጅ እንደ ዳሰሱት ፡ በጆሮ በቅርብ ሆኖ እንደ ሰሙት አድርጎ ፡ በጠቅላላው ግዙፍ አድርጎ የሚያቀርብ የድርሰት ዐይነት ነው ። ለዚህ የድርሰት ዐይነት ከሌሎች የድርሰት ዐይነቶች ይልቅ በቃላትና በሐረግ አመራረጥ በኩል ብዙ ጥረት ማድረግ ይኖርብናል ። ነጋድራስ አፈወርቅ ገብረየሱስ እንደሚሉት ፡ "... አማርኛው ቅልጥፍጥፍ ያለ ፡ ላንደበት የተስማማ ፡ ለጆሮ ያልገለማ ፡ ላንባቢው የሚመች ፡ ለሰሚው የማይሰለች እንዲሆን አድርጎ መጻፍ ነው" ማለታችን ነው ። ባጭሩ ሠዐሊ ሥዕሉን እንዲያምርለት ፡ የሰውን

መንፈስ እንዲማርክለት ለማድረግ እንደሚጥር ሁሉ ፡ ሥዕላዊ ድርሰትንም የሚጽፍ ሰው አነጋገሩን ለዛ ፡ ውበትና ጣዕም ያለው በማድረግ በአንባቢ ሕሊና ውስጥ እንዲቀረፅ ለማድረግ መጣር አለበት ። በዚህ የድርሰት ዐይነት የሚፈለገው ፡ ሐሳብን በተስተካከለ አማርኛ ማስተላለፍ ብቻ ሳይሆን ውብ በሆነና በሚያስደስት አነጋገር ጭምር መግለጽ ነው ።

ለምሳሌ ፡ የሚከተሉት ሁለት ምንባቦች ከሥዕላዊ ድርሰት የሚቆጠሩ ናቸው ።

ሀ እንደ ገባ አብሮት የገባው ሁሉ ደህና ቦታ ፍለጋ እየጣለው ወደ ላይ ሲሮጥ ፡ እበሩ አጠገብ ክፍት ቦታ ስላገኘ ሳይጋፋ ለመውጣትም እንዲመቸው ቶሎ ብሎ እዚያው ተቀመጠና መብላቱን ትቶ አዳራሹንና የግብሩን ሥነ ሥራት ይመለከት ጀመር ። የዳራሹ መጠን በወርዱም ሆነ በቁመቱ እሱ ከተቀመጠበት ሆኖ ዳርቻውን አጣርቶ ለማየት አይቻልም ። ልክ በመግቢያው በር አንፃር ወደ መጨረሻው ሲል ባንድ ከፍተኛ ድልዳል ላይ ከፊት በኩል በሰፊው ግልጥ የሆነ ጠርዙ ሁሉ በወርቅ የተከፈፈና ራሱም ወርቀ ዘቦ ግምጃ የሆነ ስፋቱ ካንድ መጠነኛ ቤት የማያንስ አጐበር ይታያል ። እዚያ አጐበር ውስጥ እንዲሁ በወርቅና የቀለሙ ህብር የብርሃን ጸዳል ተከትሎ እየተለዋወጠ ዐይን የሚያሳስት ሀር ያጌጠ በጣም ከፍ ያለ ዙፋን ተዘርግቶ በዚያ ላይ አንድ የለበሰው ልብስ እንደ ጸሐይ ጮራ ዐይን የሚለማጥ ሰው ተቀምጦዋል "አአ...! እኒያ ያለ ጥርጥር ጃንሆይ ናቸው" አለ በሃብሀ ። ከዙፋኑ አካባቢ

እድልዳሉ ላይ የተቀመጡት ሰዎች እንደ ጾደቂ ነፍሳት ከጌታቸው ተድላ ደስታ አብረው የሚካፈሉ መስለው ይታያሉ ። ስጋውን በወሳንሳ ሁለት ሁለት የስጋ መልከኞች ቀሚስ አልብሰው እየተሸከሙላቸው ጠጁ ባሳላፊዎች እጅ የበሰለ እንኮይ መስሎ ተንገርሮ እየቀረበላቸው በጸጥታ ሲበሉ ሲጠጡ በውነት ደስ ያላቸው ይመስላሉ። ከዙፋኑ አቅራቢያ ድልዳሉን ከበው የቆሙት አምዶች እንኩዋ ልዩልዩ ቀለም ባለው ጨርቅ ተሸልመው ከሩቅ ሲታዩ ላይን እጅግ ደስ ያሰኛሉ ። ከዙፋኑ ራቅ ከድልዳሉ ዝቅ እያለ ሲሄድ ግን የሁሉም አይነቱ ይለወጣል ። ከሁሉ አስቀድሞ ከድል ዳሉ በታች አዳራሹን በወርዱም በቁመቱም ከዳር እስከ ዳር የሞላው ሕዝብ አንዱ በሌላው ላይ እየተደረበ ሰፍሮ የሚተራመስ የንብ ሰራዊት እንጂ በተራ ተቀ ምጦ የሚበላና የሚጠጣ ሰው አይመስልም ። ስጋውን መልከኞቹ ሙዳ ሙዳ አድርገው እየቆራረጡ በሳጠራ ሞልተው አሸክመው ያመጡና ከሩቅ እየወረወሩ አን ዱን ፊቱን ሌላውን ደረቱን ሲሉት ልበኛ ቀልቦ ያስቀረዋል ። የዘነጋ አምልጦት እመሬት ይወድቅበ ታል ። ጠጅ አሳላፊዎች ጠላት እንደሚያሳድዳቸው እየተጣደፉ ጠጁን በኩባያ እየቀዱ ሲያድሉ በሚጠ ጡት ሰዎች እጅ እስኪደርስ ግማሹ ያክል በሰውነታቸ ውም በልብሳቸውም ይፈሳል ። ወዲያው የተረፈውን ቢጨርሱም ባይጨርሱም ላልደረሰው ለማድረስ ኩባያ ውን ከጃቸው ነጥቀው ይወስዱባቸዋል ። ይህ ሲሆን ፡ የኩባያውና የቢላዋው ኩዋኩዋታ ፡ ያሳላፊውና ያቅራ

ቢው ያጋፋረው ጫጫታ በውነት ራስ ያሳምማል ። አዳራሹ ውስጥ የቆሙትን ወጋግራዎች እየተደገፉ የቆሙ ብዙ አዝማሪዎች አሉ ። ነገር ግን እጃቸው መሰንቆውን ሲገዘግዝ ያንገታቸውም የደም ስር ተገትሮ አፋቸው በሙሉና በከፊል ሲከፈት በማየት የሚያዘምሩ መሆናቸውን ከመገመት በቀር የመሰንቆው ሆነ የነሱ ድምጽ በጭራሽ አይሰማም ። እንዲሁም ጥሩምበኞች እምቢልተኞችና መለከተኞች እያደገደጉ ተደርድረው መሳሪያቸውን በያፋቸው ለማበው ጉንጫቸው እንደፊኛ ተነፍቶ አይናቸው ፈጦ የደም ስራቸው በየግንባራቸው ተገትሮ ሲታዩ ሁሉም በየመሳሪያቸው ሲጫወቱ፤ ፎቶግራፍ የተነሱ ምስሎች እንጂ ያነለት እዚያ ቆመው የሚነፉ ነፍስና ስጋ ያላቸው ሰዎች አይመስሉ ።[7]

ለ — ቤቱን የዝምታ አዘቅት ውጦታል ። ከዚያ ዝምታ በዝምታ የሚመነጨው የሙዚቃ ቃና መጨረሻ የለውም ። ነፍስን በሀሴት ሊያወራጭ አእምሮን ኮርኩሮ ሀሳብን በስልት ሊያስደንስ ይችላል ።

አበራ ወርቁ ፡ በዚያ መጨረሻ በሌለው ዝምታ ተውጦ ሙሉ የሌሊት ልብሱን ለብሶ እንደ ልማዱ የጣት ጥፍሩን በጥርሱ እየከረከመ ወዲህ ወዲያ በመንጐራደድ ለገላው ያሞቀው ውሀ ወደ ገንዳው እስኪወርድለት ድረስ የወተሮው ባልሆነ ትእግስት ይጠባበቃል።

---

7. ሐዲስ ዓለማየሁ ፡ ፍቅር እስከ መቃብር ፡ ብርሃንና ሰላም ማተሚያ ቤት ፡ ስድስተኛ እትም ፡ 1977 ፡ ገጽ 447  449

ቧንቧው እንፋሎት ብቻ ስለሚተፋ ወደገንዳው የሚወርደው ውሀ ዝናብ ዘንቦ ካባራ በኋላ በስንበሌጥ ላይ ኮለል ኮለል እያለ እንደሚወርድ ጠፊጠፍ ስልት እየጠበቀ አንድ ባንድ ይንጠባጠባል ።

"ትኩስ የህይወት ጠብታ ፡ ትኩስ ፡ ወፍራም የህይወት ጠብታ" የሚል ሀሳብ ላንድፍታ አእምሮው ውስጥ እንደ መብረቅ ብልጭ ብሎ መልሶ ድርግም አለ። የአበራ አእምሮ ካንድ ሀሳብ ወደሌላ ሀሳብ ስለሚጋልብ አንድ ነገር በተለይ ወስዶ እስከ መጨረሻው ድረስ ሊያስብበት አይችልም ። ለዚህ ነበር ባለቅኔ፡ ወይም ደራሲ ፡ ወይም ሰአሊ የመሆን ተስፋውን ውስጡ ቀብሮ ያስቀረው ። ነፍሱ ግን ራሷን ባንድ ነገር ለመግለጥ ዘለአለም እንደዋተተች ፡ እንደቃተተች ትኖራለች ። አእምሮው ወዲያና ወዲህ እንደሚባክን ስለሚያውቅ አዘውትሮ ፡ "ሀሳብ መጨረሻ የለውም ፡ ቁም ነገሩ መኖር ነው ፡ የኑሮን ጣእም ማወቅ ። ሀሳብ የፈጠረው ግብ ካልደረሰ ውጤቱ ያው ነው ፡ ምሬትና ብስጭት ። አዎን ፡ ሌላ ምናለና!" ይላል ።

አንድ ትልቅ ወፍራም ጥቁር ዝንብ ከየት መጣ ሳይባል እንግዳ ቤት ገብቶ ጥዝዝ ... እያለ አንዴ ከኮርኒሱ ጋር ፡ አብዛኛውን ጊዜ ከመስኮቱ መስተዋት ጋር ፡ አንዳንዴ ደግሞ ከተንጠለጠሉት ባለአራት ጡት መብራቶች ጋር እየተጋጨ ክፍሉን ውጦት የነበረውን ከባድ ዝምታ ባንዳፍታ አደፈረሰው ። የዝምታው ሙዚቃ ስልቱን አጣ ። አበራ መንጉራደዱን ትቶ ዝንቡን ለመግደል ይሯሯጥ ጀመር ። የጧት ካቦርቱን

አውልቆ ዝንቡ መስኮትና ኮርኒሱ ላይ ሲያርፍ፡ ለመግ ደል አንድ ሁለት ጊዜ ከሞከረ በኋላ ጥዝዝ ... እያለ ሂዶ መብራቱ ላይ በማረፉ የሚያደርገው ነገር ጠፍቶት ወደላይ አንጋጦ ለጥቂት ጊዜ ተመለከተውና ተስፋ እንደ መቁረጥ ብሎ ራሱን ነቀነቀ ። "አሀ" አለና ሂዶ መስኮቱን ከፍቶ ይጠብቀው ጀመር ። እሱም እንዳሰ በው ፡ ዝንቡም በበኩሉ ይጠብቅ የበረውን መውጫ ቀዳዳ ያገኝ ይመስል ጥዝዝ ... እያለ ሹልክ ብሎ ወጣ ። ከውጭ የሚመጣው ሁካታ ተወርውሮ ጆሮውን መታው ። የመኪና ጋጋታ ጡሩምባ ፡ የበጎች ጩኸትና የሰዎች ድምጽ ባንድነት ሲሰማ የኔ ማኑኤል ሆስፒታል እብዶች ተሰብስበው ያቋቋሙት የሙዚቃ ጓድ ይመ ስል ጆሮ ይጠልዛል ። ቶሎ መስኮቱን ዘጋ ። "እኔ ግን መውጫ ቀዳዳ የለኝም!" አለ ዝንቡን አስታውሶ ።[8]

6·4·3 <u>ገላጭ</u>

ገላጭ የሚባለው የድርሰት ዐይነት አንድ ነገር እንዴት እንደሚሠራ ወይንም እንደሚፈጸም የሚያመለክት ወይንም የሚመራ የድርሰት ዐይነት ነው ። አንድ ሰው አንድ ቤት ወይንም መኪና እንዴት እንደሚሠራ ለመግለጽ ሲፈልግ የሚገልጽበት ጽሑፍ ወይንም ገላጭ ወይንም መምሪያ ሊባል ይችላል ። በዚህ ድርሰት ዐይነት ስለ ማናቸውም ነገር ለማስረዳት ስንፈልግ አንባቢውን ምንም እንደማያውቅ አድርገን ገምተን ማንኛውንም ጥቃቅን ነገር ሁሉ በዚሁ ጽሑፍ ተመርቶ እንዲያውቀው ወይም እንዲሠራው ለማድ

---

8 በዓሉ ግርማ ፡ <u>ከአድማስ ባሻገር</u> አርቲስቲክ ማተሚያ ቤት ሦስተኛ እትም 1967 ገጽ 5—7

ረግ መጣር አለብን ።

## የቀንበጥ ማራባት ዘዴ

ብዙ ተክል ቅጥዩን ብቻ ቆርጦ ምንም ስር ሳይኖርበት በትክሉ የተተከለ እንደሆን መሬቱ የራሰ ከሆነ ይጸድቃል ። እንደዚህ የሚረቡ አሀያ ፡ ጉርን ፡ ኮሶ ፡ ቁልቋል ፡ ቅንጭብ ፡ ቀጋ ፡ ጽጌረዳ ሌሎችም ብዙ ናቸው ። ነገር ግን እነዚህን ሁሉ እንዲጸድቁ ለማድረግ ትንሽ ጥንቃቄ ያስፈልጋል ። የሚቆረጠው ቅጣይ እርዝማኔው አንድ ክንድ ያህል ሆኖ ያውም እጅግም ለጋ እጅግም የጠነከረ ሳይሆን በሰላ መሳሪያ ከላይም ከታችም ወገን በሸላች ተቆ ርጦ ከላዮቹም 23 አይኖች ጉንቁሎች (ጕንቁሎች) ያሉበት ሆኖ ሲተክልም ከአፈሩ ውስጥ ጋደም ብሎ እንዲተኛ ጉንቁሎቹም አንድ ሁለቱ ያህል ከአፈር በላይ እንዲሆኑ ያስፈልጋል ። እንደዚህ ሆኖ ከተተ ከለ በኋላ እንዳይጠማው ውሀ ማጠጣት ነው ። ፀሐይም እንዳይጎዳው እየተመለከቱ የሚያስፈልግ ቢሆን ጥላ ማጥላት ነው ።

የቀንበጥ ማራባት ዘዴ ግድ ከመሬት ላይ እንዲሆን አያስፈልግም ። አፈሩን በታኒካ ወይም በሳጥን አድርጎ ቢተክሉት ይሆናል ።

ገበሬ ይኸን ተመልክቶ እየፈለሰፈ እያሻሻለ እየሞከረ የበለጠ ዘዴ አግኝቷል ። መቸም ቅጥዩ ሁሉ የሚፈልገው ምግብ ነውና የሚስማማውን ምግብ ካገኘ ከዛፍ ላይም ቢሆን ይበቅላል ። ቅጥዩ ሁሉ ከግንዱ ላይ ማደጉ የሚያስፈልገውን ምግብ

ከግንዱ ላይ በማግኘቱ ነው ። ስለዚህ ጉማው ከሆነው ዛፍ ላይ የግንዱን ቅርፊት ሰንጥቆ ቅጥዩን እላዩ ቢያጣብቁት ይጠድቃል ። ነገር ግን ይኸው ሲደረግ ጥንቃቄ ያስፈልጋል ። የግንዱም የቅጥዩም የሁለቱም ልጦቻቸው በተሰነጠቁበት ወገን በትክ ክል እንዲገናኙ ያስፈልጋል ። ወዲያውም እንደተያ ያዙ ሳይንቃንቁ እንዲሰነብቱ ባንዳች ነገር ማስተሳ ሰር ያስፈልጋል ። የቅጥዩም የግንዱም ቁስላቸው እስቲሽርና እስቲያያዙ ድረስ (አንድ አካል እስቲ ሆኑ ድረስ) ተቀጽላውን ፀሐይም ነፋስም እንዳያጠ ቃው መመልከት ነው ። እንደዚህ ሆነው እስተሳም ንት የቆዩ እንደሆን ቅጥዩ ይጸድቅና ተቀጽላ ይሆ ናል ። የዚህ አይነት የማራባት ዘዴ ክትባት ተብ ሏል። የክትባት ዘዴ የሚከናወነው በተለየ ወቅት ነው ። በብላጊ ወቅት ይሻላል ።[9]

### 6·4·4 አመዛዛኝ/አከራካሪ

አመዛዛኝ ወይም አከራካሪ ድርሰት ሁለት ወይንም ከዚያ በላይ የሆኑ ተቃራኒ ሐሳቦች በማመዛዘን በክፉም ሆነ ደግ የትኛው እንደሚበልጥ ፡ እንደሚሻል እንደሚያይል እንደሚከፋ ወዘተ... የሚያሳይ የድርሰት ዐይነት ነው ። በዚህ የድርሰት ዐይነት ውስጥ የጸሐፊው ዋና ዓላማ ሌሎችን ለማሳመን ፡ ለመርታት አንዱን አንኳሶ አንዱን ለመደገፍ ነው ። ስለዚህ ከሌሎች የድርሰት ዐይነቶች ይልቅ ይህ ዐይነቱ

---

9 ፊታውራሪ ተክለ ሐዋርያት ፡ ስለእርሻ ትምህርት ፡ ግርማዊ ንጉሥ ተፈሪ መኮንን ማተሚያ ቤት 1922 ፡ ገጽ 121

ድርሰት ሰውን የሚያሳምኑ አጥጋቢ መረጃዎች እንደሚጠይቅ መገንዘብ ይጠቅማል ። አንዳንድ ተማሪዎች ሐሳባቸውን በክርክር መልክ አጠንክረው ሲያቀርቡ በተከራካሪያቸው በኩል ሊመጣ የሚችለውን ጥያቄ ቸል ይሉታል ። ወይንም ሊመጣ እንደማይችል ይቆጥሩታል ። ያመዛዛኝ ድርሰት ዓለማ የሚያከራክሩ ሐሳቦችን አመዛዝኖ ተገቢውን ፍርድ መስጠት ስለሆነ በሁለቱም በኩል ሊቀርብ የሚችለውን በጎም ሆነ ክፉ ነገር አጉልቶ ማየቱ ይገባል ። ለምሳሌ የሚከተለው ካመዛዛኝ ድርሰት ሊቆጠር ይችላል ። የሚያወዳድረውም ለራሱ አሳቢንና ለሰው አሳቢን ነው ። ይሁንና የሚወዳደሩት ነገሮች ተመጣጣኝ አለመሆናቸውን ማስተዋል ያሻል ።

ለራሱ አሳቢ በየጊዜው ያፈራውን በልቼው ፡ አጊጬበት ተድላ ደስታ አይቼበት ሁሉንም ጨር ሼው ልሙት ሲል ለሰው አሳቢ በጊዜው ለሰው ቸርነት ማድረጉን ሳያቋርጥ ከሞትሁ በኋላ ደግሞ ልጆቼ የሚያድጉበት ፡ ካደጉም በኋላ የሚማሩበት ትምህርታቸውን ሲጨርሱ የሚዳሩበትና ጎጆ የሚ ወጡበት ገንዘብ ያስፈልጋቸዋል ሲል ያለዕረፍት ይሠራል ። ለራሱ አሳቢ "እኔ ከሞትሁ ሠርዶ አይብቀል" ባለችው ባህያዋ ተረትና ፍልስፍና ሲያገዝ ለሰው አሳቢ ይኸን ፍልስፍና መቀበል ይቸግረዋል ። በዚህ ፋንታ የማይንቀሳቀስ ሀብት ወይም የሚንቀሳቀስ ጥሪት እኔ ሳላቋቁም ድንገት የሞትሁ እንደሆን ቤተሰቤ የሰው እጅ በማየት ይቸገራል የሚል ሥጋት ያድርበታል ። ስለዚህ

ለራሱ የሚበቃ እያለው ለተወላጁ ቤትና መሬት ወይም ጥሬ ገንዘብ ለማከማቸት ሽቅብና ቁልቁል እየሮጠ ያለዕረፍት በሥራ ይዋትታል ። ለራሱ አሳቢ እሱን ከተመቸው በቅርቡም ፡ በሩቅም ያለ ዘመዱ ቢቸገር ግድ የለውም ።[10]

እነሆ እንዳነበብነው ፡ ለሰው አሳቢ የሚለው ወገን ክርክሩ ስለአደላ አርእስቱ ራሱ ተገቢ መከራከሪያ ላይሆን ይችላል ። የሚከተለው ግን ከዚህ የጠነከረና አከራካሪ ጽሑፍ ነው ። የሚናገረውም ስለ እምነት አስፈላጊነት ነው ። የተጠቀሰው የፍልስፍና ትምህርት ከሚለው ከየማን ገብረ ማርያም ከአንደኛው መጽሐፍ ነው ።

... እምነት ለማናቸውም ነገር የምታገለግል ትልቅ መሣሪያ ናት ። ሳይታወቅን ማናቸውንም ነገር የምናደርገው በርሷ በኩል ሆኖ ይገኛል ። ይህንንም የምንረዳው ተጠንቅቀን ስናስተውልና ያለ አድልዎም የፈረድን ጊዜ ብቻ ነው ። ያን ጊዜም ያለርሷ ምንም ነገር ሊሳካልን እንደማይቻል ፈጥነን እንረዳለን ። ካላየን አናምንም የሚሉት ተጠራጣሪ ዎችም እንኳ ቢሆኑ ባፋቸው ይክዱዋት እንጂ በሥራቸው ሊክዱዋት አልቻሉም ።

በማናቸውም የዕውቀት ዐይነት ውስጥ ስንኳ እምነት የምታስፈልገን መሆኗን ለመግለጽ ሲል ያሥራ ስድስተኛው ክፍለ ዘመን ኡጎ ግሮቲዮስ የተባለ አንድ ሊቅ ሲናገርም ያለ እምነት ማናቸ

10 ተክለ ጻድቅ መኩሪያ ፡ የሰው ጠባይና አብሮ የመኖር ዘዴ ፡ ትንሣኤ ዘጉባኤ ማተሚያ ቤት ፡ ሦስተኛ እትም 1950 ገጽ 143

ውም ነገር ወዳቂ ነው ፡ እምነት የማታስፈልግበት ስፍራ የለም ። ማናቸውም የዕውቀት ዐይነት ታሪክም ቢሆን ሳይንስ ሁሉም በየበኩላቸው እምነትን በውስጣቸው ያስገባሉ ። ያለ እምነት የተመሠረተ አንድም ዐይነት ዕውቀት አይገኝም ብሎ ተናግሯል። በእውነቱ የዚህ ሰው ንግግር እውነትን የተመረኰዘ ነው ብንል ስሕተት አይሆንም ።

እነሆ ለምሳሌ ፡ ብዙ ተሻግረን ሳንሔድ ታሪክ የተባለውን ትምህርት እንውሰድ ። በዚህ ትምህርት ውስጥ የትልቁ እስክንድርን የትልቁ ናፖሊዎን የሌሎችም ቁጥራቸው የበዛ የታላላቅ ፈላስፎችና የፖለቲካ መሪዎች የአርበኞችና የጻድቃን ሰዎች የሕይወት ታሪክ ፡ እንደዚሁም ከዚህ በፊት ልዩ ልዩ ከተሞች ሕዝቦች ሌሎችም ነገሮች ሁሉ እንደነበሩ በሰፊው ይነገርበታል ። ነገር ግን ከዚህ ጥቂት ቆም ብለን ብናስተውል ፡ የነዚህን ሁሉ ታሪክ ሰምተን እንደ እውነትም አድርገን እንድንቀበለው የምታስችለን እምነት ባለችው ነገር መሆኗን ለመረዳት ይቻላል ። ስለዚህም የማላየውንና የማልዳስሰውን ነገር አልቀበልም የሚል ሰው እነሆ ከርሱ በፊት የነበረውን ሁሉ ታሪክ (አላየውምና) የሚክድ ሰው መሆኑ ነው። ወደፊት የሚወለዱት ልጆቻችንም የርሱን ሐሳብ (ምሳሌ) ይዘው የወጡ እንደሆን የምንጠረጥር መሆናችን የተረጋገጠ ነው ።

በእውነቱ ታዲያስ ይህ እንደቀልድ አይቆጠር ምን? እስተዋይ አንባቢ ሆይ ፡ እስቲ አንተም ፍረድ ፡

እንዲህ ያለው አስተያየት ነገርን ከሚያመዛዝንና አእምሮው ከተስተካከለ ሰው አንደበት የሚወጣ ነውን? በእውነቱ አስተዋይ እንደ መሆንህ መጠን ይህን ነገር አንተም እንደምትቃወመው የማይጠረ ጠር ነው ። ያለ እምነት በእውነት ምንም ነገር ለመፈጸም አንችልም ። ማናቸውም የዕለት ተግባራ ችን ሁሉ የሚከናወነው በእምነት መሆኑን ለመካድ የማይቻል ነው ። ለምሳሌ ፡ በድልድይም ላይ ብንሻገር በመኪናም ብንሄድ ፡ በአይሮፕላንም ብንበር ፡ እህልም ብንዘራ ሌላም ማናቸውንም ነገር ብናደርግ ፡ እምነትን ተመርኩዘን ነው ። ይኸውም ይህን ሁሉ ስናደርግ አደጋ ሳያገኘን ካሰብንበት ስፍራ በሰላም እንደርሳለን ብለን ልባችንን ሞልተን ነው ። እንደዚሁም የምንዘራውም እህል ቢሆን እንደዚያው ካፈር ውስጥ እንደ ተቀበረ ሳይቀር ቀስ በቀስ አድጎ ሁለትና ሶስት እጅ እናተርፋለን ብለን ነው ወደ አፋችን በማድረግ ፋንታ ከመሬት ላይ የምንዘራው ።

እምነት በጣም ያጣ ሰው የለም ። እምነት ሳይኖረን በችግር እንኖር ነበር ። በሰው ቃል ችሎት እናምናለን ። ወላጆቻችን እንዳያታልሉን እናምና ለን ። ፀሐይ በጊዜው እንዲወጣ ፡ ዝናብም በወራቱ እንዲዘንብልን ተስፋ አድርገን እናምናለን ። ወደማ ናውቀው ከተማ በገባን ጊዜ ከባላገሮች አንዱን አግኝተን የምንፈልገውን ቤት እንዲያሳየን ስንጠይ ቀው አቅንቶ እንዲያሳየን እናምናለን ። ስታመም

ወደ ሐኪም እሄዳለሁ ። የሚጠቅመኝን መድኃኒት እንዲሰጠኝ አምናለሁ ። ተጨንቄ ምክር ሲያስፈልገኝ ርሱ እንዲረዳኝ አምኜ የሚለኝን ሁሉ ለመቀበል ወደ አስተዋይ ሰው እሄዳለሁ ። ሁል ጊዜ በገበታ አጠገብ ተቀምጠን ምግብ ሲቀርብልን በእምነት እንበላለን ። ይህን ማለቱ ምግባችንን ያቀረበልን ሰው መርዝ ቀላቅሎ እንዳይፈጀን አምነን ያለ ፍርሀት እንበላለን ። ገበሬ እርሻውን እያረሰ ፀሐይና ዝናም በየጊዜው እንዲሆንለት አምኖ በተስፋ ይዘራል ።

ሙሉ ህይወታችን በእምነት ስለ ተመሠረተ ሰውን ሳናምን ልንኖር እንደማይከናወንልን አስተዋይ ያውቃል ። ባልንጀሮቻችንን ባናምን በሥራችን ሁሉ ተንጉለን እንቀራለን ፡ ደግሞ በነገሩ ሁሉ አይሳካልንም ። በምንሰራበትና በምንሄድበት ነገር እንዴት አድርገን እንመርምር? ሳንበላ ምግባችንን የመረመሩ ዐዋቂዎች ለመጥራት ሁል ጊዜ የሚያስፈልገን ቢሆን ስንት የሚያስለች ነገር በሆነብን ። መርከቡ ወዴት እንደሚሄድና መቼ እንደሚነሳ አለቆቹ ባያመለክቱን ወይስ ቃላቸውን ባናምን እንዴት አድርገን በመርከብ መንዝ እንደፍራለን ።

ያለ እምነት ለመኖር የማይቻል ነው ። ስለዚህ ያለ እምነት የሚኖር ሰው የለም ። እምነቱ ሥራችንንና አኗኗራችንን ሁሉ ያቃናል ፡ ይመራል ። ሀኪሙን ብተማመነው ምክሩን አምኜ እንደሚለኝ አደርጋለሁ ። በወዳጁ ፍቅርና ማስተዋል ባምን

ምክሩን እሰማለሁ ። ትምህርትም ብፈልግ ፍቺውን ተርጉሞ ወደሚያስረዳኝ ብልህ ሊቅ እሄዳለሁ ። ከኔ አብልጦ እንደሚያውቅ ተረድቻለሁና ፤ የሚያስደን ቀኝን ለማስተዋል የሚቸግረኝን ጥበብ ከሱ እቀበላ ለሁ ። [11]

የሚቀጥለው ጽሑፍ ለአካራካሪና ለአመዛዛኝ ድርሰት ተጨ ማሪ ምሳሌ ሊሆን ይችላል ።

በነገር አልተስማማንም መሰለኝ ። እኔ የም ለው የምኞታችን ዐላማ መልካምነት የማይጠረጠር ሆኖ ግልጽ ሆኖ የሚታየውን ነው ። ለምሳሌ ስላገር ፍቅር ጉዳይ የግል አገር የለንም ሰርተን የምንኖር በት ሁሉ አገራችን ነው የሚሉትንና እንዲሁም ሰው በተፈጥሮ ቀና ነው ያለጥቅም ያለ ግዴታ አስቦ አውቆ ሊሰራና ርስ በርሱ ሊጠቃቀም ይችላል የሚሉትን ሰዎች ያሳባቸውን መልካምነት ለመከራ ከር ሳይሆን ፍጻሜው ግን የሚያደግት በመሆኑ አልቀበላቸውም ። እንደዚሁም ጦርነት በህዝቦች መካከል ይቀራል የሚሉት አሳቢዎች በስህተት ላይ ይሄዳሉ ። ምክንያቱም ሰው በተፈጥሮው ራሱን አብልጦ መውደዱን እንደማይተው እንዲሁም አገሩ ንና ወገኑን ከሌላው ሰው ይበልጥ መውደዱና ለጥቅሙ ሲል ጦርነት ማንሳቱ የማይቀር ስለሆነ ነው ።

---

11 የማነ ገብረ ማርያም ፡ የፍልስፍና ትምህርት 1ኛ መጽሐፍ ብርሃንና ሰላም ማ/ቤት 1954 ገጽ 204 — 206

እንደዚህማ ከሆነ ሰው የራሱን ጥቅም አሳልፎ ለመስጠትና ያላንዳች ጥቅም ተግባሩን ለመፈጸም አይችልም ማለትዎ ነው? እንዲህ ከሆነስ ፈላስፎችና ጠቢባን ሁሉ ሌት ተቀን ለራሳቸው ጥቅም ለሌለው ስራ የሚደክሙትና ህይወታቸውንም እስኪያጠፋው የሚታገሉት ምንድናቸው? እንኪያስ የሰውን ልቦና ባጭሩ ከወሰኑት ሰው ለመቼውም ቢሆን ከእንስሳነት ጠባዩ የማይላቀቅ በጠባቡ የተወሰነ ከንቱ ፍጥረት ነው ማለት ነው ። ነገር ግን የሰውን ልጅ ጠቅላላ ታሪክና አስተዳደጉን ስመለከተው ይህን አያሳምነኝም ።

ሰው በድንገተኛ ስሜቶች መንፈሱ ሞቆና ተቀስቅሶ እንደ ወኔ ወይም እንደ ፍቅር የመሰሉ ሀይለኞች (ፖሲዩን) የተሰሙት እንደሆን ብዙ የሚደነቅ ጀብዱ ሊሰራ ይችላል ። ነገር ግን አብዛኛውን ጊዜ ይህን ሲያደርግ ከሰውነት ጠባይ ወጥቶ እኮ ነው ። ሰው እንደ ማንኛውም ሕይወት ያለው ፍጡር ሁሉ የመጀመሪያ ተግባሩ የራሱን ሕይወት መጠበቅ ስለሆነ በተፈጥሮው ራሱን ወዳድ ነው ። የራሳቸውን ስሜት አሸንፈው ተፈጥሮአቸውን ገዝተው ለጽድቅ ብቻ በይገባል ያላንዳች ተስፋ ያላንዳች ጥቅም የሚሰጡ ሰዎች አሉ ብዬ ለማመን አልደፍርም ፤ ቢኖሩም ቅሉ ከሰውነት ደረጃ ወጥተዋል እላለሁ ።

የሆነ ሆኖ ክርክራችንን የጀመርነው ላገርዎ ማሰብና ወገኖችዎን መርዳት ይገባዎታል አይገባዎ

ትምን በማለት ስለ ሆነ እንደኔ አስተያየት ዛሬ የርስዎ ተግባር ላገርዎና ለወገኖችዎ መስራት መሆን አለበት ።

ይሁን እንጂ አገርና ወገን ማለት ምንድነው? ከሌላይቱ አገር ለይተህ የምታያት የራስህ አገር አለችን? ከሌሎችም ሰዎች ለይተህ የምታያቸው የራስህ ወገኖች አሉን ብለው ካሉኝ ይህች "የራስ የግል አገራችን" ናት ለማለት ምን መሰረት አለን? እንዲያው ከተወለድሁባት ርስት ስላለኝ እናት አባቴ ስለሚኖሩባት አይደለምን? ታዲያስ ይህ የሚበቃ ምክንያት ሊሆን ነውን?

አገር ማለት ወገን ማለት ቀላል ነገር አይደለም ። ያገርን ፍቅር የሚፈጥረው ጥቅም ብቻ አይደለም ። አገር ከቀድሞ አባቶች ዠምሮ ሲወርድ ሲዋረድ የተላለፈልን ልዩ ልዩ ጠባዮችና ልማዶች ናቸው ። አገር ማለት ያ ያባቶቻችን አጥንት የተከሰከሰበት ያ ያባቶቻችን ላብና ደም የፈሰሰበት ነው ። ያ አባቶቻችን የተከራከሩበት የሞቱበት ያቆዩን መታሰቢያና ምግባር መብትና ሃይማኖት ነው ። አገር ማለት በጠቅላላው ያገራችን ታሪክና መታሰቢያ ሁሉ ነው ።[12]

---

12 ግርማቸው ተክለ ሐዋርያት ፡ <u>አርአያ</u> ብርሃንና ሰላም ማ ቤት 2ኛ እትም 1960 ገጽ 39 40

## 6·4·5 የድርሰት ዐይነቶችን መደባለቀ

አንድ ጸሐፊ ከፈለገ ድርሰቱን ከተጠቀሱት መንገዶች ባንደኛው ብቻ ሊጽፍ ይችላል ። ይሁንና አንድ ጸሐፊ አንዱን መንገድ ብቻ ተከትሎ እንዲጽፍ የሚያስገድደው ሕግ የለም። ሁለቱንና ወይንም ሦስቱን የድርሰት ዐይነቶች የማያቀላቅል ድርሰት ማግኘት ሳያዳግት አይቀርም ። ማለት በአንድ ድርሰት ውስጥ ተራኪም ፡ ሥዕላዊም ፡ ገላጭም ፡ አካራካሪም የድርሰት መንገድ ሊገኝ ይችላል ። እንዲያውም የግድ ባንድ ዐይነት ምክንያት ለምሳሌ በትእዛዝ አንዱ ዐይነት ድርሰት እንዲጻፍ ካልተፈለገ በስተቀር በአንድ ድርሰት ውስጥ ልዩ ልዩ አጻጻፍ መንገዶች ሲፈራረቁ ድርሰቱን እንዳያስለች ያደርጉታል ። እንደ ልማድ ሆኖ አብዛኛውን ጊዜ ተራኪና ስዕላዊ ባንድ ድርሰት ውስጥ በመፈራረቅ ይገኛሉ ። ለምሳሌ ፡ መስፍን ሀብተማርያም የሚባለው ያራተኛ ዓመት የዩኒቨርሲቲ ተማሪ የነበረ ከጻፋቸው ድርሰ ቶች መካከል አንዱን ለሥዕላዊ ተራኪ ድርሰት ምሳሌ ይሆን ዘንድ እንጠቅሰዋለን ።

> ያለፈ ነገር ሲያስታውሱት በጣም ያስገር ማል። እነዚያ ጓደኞቼ ሁሉ ዛሬ አጠገቤ የሉም ። ሆኖም ዐልፎ ዐልፎ ሳስታውሳቸው ስራቸው ሁሉ ከፊቴ ይደቀናል ። የነምትኬ ቀልድ ትዝ ሲለኝ እስቃለሁ ። የእጥናፉና የታምራት የኳስ ጥበብ ሲታወሰኝ እነሱን የሚያስንቅ ተጫዋች ከቶ ያለም አይመስለኝም ። የሰፈራችንን ቡድን ካገኑት ውስጥ የሺጥላም ይገኝበታል ። አንድ ጭኑ የሁለት

ሰው የሚያህለው የሺ.ጥላ ኳሷን ከነሰውየው እግር መምታት ልማዱ ነበር ። ግብ ለማግባት የሚመጡ ሁሉ የሺ.ጥላ ገና መንደርደሩን ሲጀምር ከቻሉ ኳሷን ነካ አድርገው አለዚያም ትተዋት ወደኋላቸው ይመለሱ ነበር ።

የሰፈሬ ልጆች እነዚህ ብቻ አልነበሩም እነ አሥራት ቂሎ ፡ እነወንድአፍራሽ ተንኮሉ ሁሉ ፡ አብረውን ይማሩ ነበር ። አሥራት ዛሬ መሐንዲስ ነው ። ወንዳፍራሽ ደግሞ አግብቶ ሁለት ወልዷል ። ያንን ሁሉ ትቶ ዛሬ ጭምት ሆኖአል አሉ ። ድሮ በኛ ተማሪ ቤት በመገረፍ ደረጃ ወንዳፍራሽን የሚያህል አልነበረም ። ትንሽም የምትወዳደረው ብርቄ ነበረች ። ብርቄ የሰዋስው ጥያቄ በመጣ ቁጥር ዘወትር ትገረፍ ነበር ። ማልቀስ የምትጀምረው ገና አቶ አስናቀ ያንን መነጽራቸውን ሰክተው "ስም ማለት ምን ማለት ነው" ለማለት ሲሰናዱ ነው ። በተለይም አንድ ቀን አምስተኛ ክፍል ሳለን ጃንሆይን "እሳቸው" ለማለት ፈልጋ "ዜይ" ብላ ገና ስትጀምር የሳቅነው መሳቅና በአቶ ሙላቱ የተገረፈችው መገረፍ ትዝ ይለኛል ።

በእንግሊዝኛ የቃል ጽሕፈት ጊዜ ብርቄና

ወንዳፍራሽ አስር አስር ሳይገረፉ ውለው አያውቁም። በነርሱ ላይ ይበረታል ለማለት ነው እንጂ ሁላችንም አልፎ አልፎ መቅመሳችን አይቀርም ነበር ። ገና አስተማሪው በሩን ከፍተው "ጉድ ሞርኒግ" ሲሉ ሁላችንም መርበድበድ እንጀምራ

ለን። ማስመሪያው ፡ መጥረጊያው ፡ ወንበር ተሸክሞ መቆሙ ፡ እጅ ወደላይ አድርጎ መንበርከኩ ሁሉ ትዝ የሚለን ያኔ ነው ። ከዚያም ምን ተጠይቆ ጥያቄው ሲጎርፍ ፡ ያጠናው እንደጥይት እሩምታ ሲያንቃቃው ፡ ያላጠናው ሲቀባጥር ዱላው ፡ ውካ ታው ፡ ይህ ነው አይባልም ።

አስተማሪው ወጣ ሲሉ ደግሞ ክፍላችን ሌላ መልክ ይይዛል ። እነሲሳይ ወደ ሰሌዳው ተንደርድ ረው ይሄዱና ሥዕል መሳል ይጀምራሉ ። እነወንዳፍ ራሽ ምትኬ ቲያትር መሥራት ይጀምራል ። እነ ኃይሉ እንግሊዝኛ እየተነጋገሩ ይንጎራደዳሉ ። ጩዋ የምንለው አርጋው እንኳ የግብረገብ አስተማ ረያችን አለቃ ኤፍሬም ሲያደርጉ አይቶ ትንሽ ቆብ ራሱ ላይ ይደፋና አስርቱ ቃላትን ካላስተማርኳችሁ ይላል ። ጫጫታው ጆሮ ያሳምማል ። እነብርቄ ፡ እነዓለሚቱ ፡ እንወንዳፍራሽ ለቅሷቸውን ትተው የደራ ወሬ ይጀምራሉ ። እነካሳ ደግሞ ትንሽ የላስቲክ ኳስ ይዘው እዚያው ቡድን ለይተው እዚያው ይጫወታሉ ። ጠመኔ ወርዋሪው ግን ልክ የለውም ። ወሬው ፡ ዘፈኑ ፡ ድብድቡ ፡ ዑዑታው ይቀጥላል ። ጥቂት እንደቆየን ከውጭ አንድ ድምጽ ይሰማል ። የሰማው ወደ መቀመጫው ሲሮጥ ያልሰ ማው የጀመረውን ሲቀጥል ሌላው አስተማሪያችን ይገባሉ ። የጩዋታው መድረካችን የነበረው ክፍል ባንዳፍታ በፀጥታ ይዋጣል ። ሆኖም ስናደርግ የነበረውን ሁሉ ክፍላችን ደብቆልን አያውቅም ።

እንዲህ አይነቱ ነገር በተፈጠረ ቁጥር መምህራችን የሚደርሱት ጠመኔ ማጥፊያው ወንበራቸው ላይ ሆኖ ፡ መጥረጊያው ሰሌዳውን ተደግፎ ፡ ጠረጴዛቸው በሩ ድረስ ተጎትቶ የአንዳንዶቻችን ፊት በጠመኔ ተለውሶ ፡ የአንዳንዶቻችን ኮት መሬት ወድቆ ፡ ሁላችንም በመደናገጥ ቁና ቁና ስንተነፍስ ነው ። መምህራችን ከገቡ በኋላ ያንን አለንጋቸውን እንደ ጨበጡ እጆቻቸውን ከኋላቸው አጣምረው ግንባራቸውን ኮስተር አድርገው ትኩር ብለው ያዩናል ። ወዲያውም በቀስታ ድምጽ የተለመደውን "ጉድ ሞርኒግ" ካሰሙ በኋላ ጥፋተኛውን ለመለየት ጉዳዩን ከሥሩ ለማጣራት ከኛ ጋር ሲራገጥ የነበረውን ያንኑ የፈረደበትን የክፍል አለቃ መጠየቅ ይጀምራሉ ።

# ምዕራፍ ሰባት

7. ሥርዓተ ነጥብ

- አንቀጽ ዋና ዋና ፍሬ ሐሳቦችን በቀላሉ ለመረዳት እንዲቻል እየከፋፈሉ ማቅረቢያ ስልት መሆኑ ቀደም ብሎ ተነግሯል ። ነጥቦችም ቃልን ከቃል ፡ ሐረግን ከሐረግ ፡ ዐረፍተ ነገርን ከዐረፍተ ነገር እየለዩ የማመልከቻ ዘዴዎች ናቸው ። በነጥብ ሳንከፋፍል ሐሳባችንን መደዳውን ብንደርድር ምን ለመናገር እንደ ፈለግን ለመረዳት አንባቢያችን ብዙ ጊዜ ይፈጅበታል ። ለምሳሌ ያህል የሚከተለውን እናስተውል።

ም·1 ባለፈው ሳምንት በየመንደሩ እያዞረ ዕቃ ይሸጥ የነበረውን ነጋዴ ባቡር ገጭቶ ገደለው ።

እነሆ በዚህ ዐረፍተ ነገር ውስጥ ቃላት በነጥብ ወይንም በቦታ መራራቅ ስላልተለያዩ ፡ ለማንበብም ሆነ ለመረዳት ጊዜ ይፈጃል ። አጻጻፋችን ይህን መንገድ ቢከተል ኖሮ በጽሑፍ ሐሳብን ለመለዋወጥ የቱን ያህል አድካሚ እንደሚሆን በዚሁ ምሳሌ መረዳት ይቻላል ።

- ቃልን ከቃል የምንለይበት ዘዴ በቃላት መካከል ሁለት ነጥብ በማድረግ ነው ። ይህን ዘዴ አብዛኛውን በአሁኑ ጊዜ የምንገለገልበት ለእጅ ጽሑፍ ነው ። ለመኪና ጽሑፍና

ለሕትመት ግን ፡ በየሁለቱ ቃላት መካከል ትንሽ ባዶ ቦታ ይተዋል ። እላይ የተጻፈው ዐረፍተ ነገር በሁለቱም መንገዶች ሲሠራ እንደሚከተለው ይሆናል ።

ሀ. <u>በነጥብ በመለየት</u>

ባለፈው ፡ ሳምንት ፡ በየመንደሩ ፡ እያዞረ ፡ ዕቃ ፡ ይሸጥ ፡ የነበረውን ፡ ነጋዴ ፡ ባቡር ፡ ገጭቶ ገደለው ።

ለ. <u>በቦታ ርቀት በመለየት</u>

ባለፈው ሳምንት በየመንደሩ እያዞረ ዕቃ ይሸጥ የነበረ ውን ነጋዴ ባቡር ገጭቶ ገደለው ።

## 7.1 <u>በጣም ተፈላጊ የሆኑ የነጥብ ዓይነቶች</u>

7.1.1 ሁለት ነጥብ (፡)
ስለሁለት ነጥብ አገልግሎት ከላይ የተነገረው ይበቃል ።

7.1.2 ነጠላ ሠረዝ (፣)
ለነጠላ ሠረዝ ሁለት ዓይነት የተለመዱ ምል ክቶች አሉን ።

አንደኛው ከሁለት ነጥብ አናት ላይ አጭር ሠረዝ (፣) በማድረግ የሚሠራ ሲሆን ፡ ሁለተኛው ደግሞ እንደ ማካፈል ምልክት በሁለት ነጥብ መካከል አጭር ሠረዝ (÷) በማድረግ

ይሠራል ። የሁለቱም አገልግሎት አንድ ስለሆነ ፡ እያንዳንዱ ጸሐፊ በመረጠው በአንዱ ዐይነት ብቻ መጠቀም ይችላል ። ሁለቱንም ዐይነት ማደባለቅ ግን ሥርዓት የለሽ ያሰኛል ። አንባቢ ሁለቱ በሚፈራረቁበት ጊዜ ለሁለት የተለያየ ሞያ የዋሉ እየመሰለው ግራ ሊጋባ ይችላል ። ስለዚህም አንዱን ብቻ መርጦ መጠቀም ተገቢ ነው ።

## * የነጠላ ሠረዝ አገልግሎት

### 7.2.1 ሀ የሚዘረዘሩ ነገሮችን መለየት

ም.52 አየለ ፡ ከበደ ፡ ፈጠነ ፡ ንጋቱና ጀማነህ የመሐሪ ጓደኞች ናቸው ።

በዚህ ምሳሌ ውስጥ የተዘረዘሩት ስሞች ያለ ነጠላ ሠረዝ መቱን ቢደረደሩ (ማለት አየለ ከበደ ፈጠነ ንጋቱና ጀማነህ...) ስንት ሰዎች መሆናቸውን ለመረዳት ያስቸግር ነበር ። ምክንያቱም አዘራዘራቸው ስም ከናባት ወይንም በነጠላ መሆኑ ስለማይታወቅ ነው ። እነዚህኑ ስሞች በተለያየ መንገድ በነጠላ ሠረዝ ብንለያያቸው የሰዎቹ ብዛትና ማንነት እንደሚከተለው ይሆናል ።

ም.3 አየለ ከበደ ፡ ፈጠነ ንጋቱና ጀማነህ የመሐሪ ጓደኞች ናቸው።

ም.4 አየለ ፡ ከበደ ፡ ፈጠነ ንጋቱና ጀማነህ የመሐሪ ጓደኞች ናቸው ።

ም.5 አየለ ፡ ከበደ ፈጠነ ንጋቱና ጀማነህ የመሐሪ ጓደኞች ናቸው ።

ም.6 አየለ ፡ ከበደ ፡ ፈጠነ ንጋቱና ጀማነህ የመሐሪ ጓደኞች ናቸው ።

እነሆ እንግዲህ የመሐሪ ጓደኞች በም.2 ውስጥ አምስት ናቸው ። በም.3 ደግሞ ሦስት ሲሆኑ በም.4 አራት ናቸው ። እንደዚሁም በም.5 እና 6 አራት ፡ አራት ናቸው ። ይሁን እንጂ፡ በየምሳሌዎቹ ቅንጅታቸው የተለያየ መሆኑን ማስተዋል ያሻል ።

የሚዘረዘሩ ነገሮች የሰው ስሞች ብቻ ሳይሆኑ ሌሎችም ብዙ ዓይነቶች መኖራቸው ግልጽ ነው ። ለምሳሌ የሚከተለውን እንይ ።

ም.7 በክፍሉ ውስጥ የሚታየው አንድ ጠረጴዛ ፡ አምስት ወንበር ፡ ሁለት አልጋ ፡ አንድ ቁምሳጥንና አንድ ባዶ የመጽሐፍ መደርደሪያ ብቻ ነው ።

### 7.2.2 ጥገኛ ሐረጎችን መለየት

ም.8 ውሃ ቀድቼ ፡ እንጨት ሰብሬ ፡ እህል ፈጭቼ ፡ እንጀራ ጋግሬ መኖር አንገሸግሾኛል ።

ም.9 ውሃ እየቀዳሁ ፡ እንጨት እየሰበርኩ ፡ እህል እየፈጨሁ ፡ እንጀራ እየጋገርሁ መኖር አንገሸግሾኛል ።

### 7.2.3 ተጣማሪን መለየት

ም.10 የጢሞ ልጅ ፡ ከበደ ነገ ይመጣል።

ም.11 አምና የተሸለመው ፡ ያ ፡ የታወቀው ደራሲ ፡ ዘንድሮም አንድ መጽሐፍ አውጥቷል ።

## 7.3 ድርብ ሥረገ

ድርብ ሥረገ ራሳቸውን የቻሉ ፡ ነገር ግን አንዱ ከሌላው ጋር ግንኙነት ያላቸው ዐረፍተ ነገሮችን ለመለየት ያገለግላል ።

### 7.3.1 ድርብ ዐረፍተ ነገርን መለየት

ም.12 ደመናው ከብዷል ፤ ስለዚህ ሳይዘንብ አይቀርም ።
ም.13 ሰው ተሰብስቧል ፤ ውይይቱ ግን ገና አልተጀመረም ።

በነዚህ ሁለት ምሳሌዎች እንደሚታየው የመጀመሪያው ዐረፍተ ነገር ከሁለተኛው በድርብ ሥረገ ሲለይ ፡ ሁለተኛው ግን በአራት ነጥብ ተዘግቷል ።

### 7.3.2 ድርብርብ ዐረፍተ ነገርን መለየት

ድርብርብ ዐረፍተ ነገር ማለት እርስ በርሳቸው ግንኙነት ያላቸው ከሁለት በላይ የሆኑ ዐረፍተ ነገሮች ተከታትለው የሚነገሩበት ዐረፍተ ነገር ነው ።

ም.14 ልብሷን ለባብሳለች ፡ ጠጉሯን ተሠርታለች ፡ ዐይኗን ተኳኩላለች ፡ ማለፊያ ሽቶም ተሸምታለች ፡ ከዚህም ወደ አንድ በዓል ቦታ ለመሔድ የተዘጋጀች መሆኗን መረዳት ይቻላል።

ም.15 ኃይሉ ከወንድሙ የተላከለትን ደብዳቤ አንብቦ ጨርሶ ጥቂት ጸጥ ብሎ አሰበ ፡ ወዲያው ጠረጴዛውን አስተካከለ ፡ ብዕርና ወረቀትም አቀረበ ፡ ከዚያም የመልስ ደብዳቤ መጻፍ ጀመረ ።

### 7.4 አራት ነጥብ (።)

ማንኛውም ዐረፍተ ነገር ድርብና ድርብርብ ዐረፍተ

ነገር ካልሆነ በስተቀር ፡ ከማሰሪያ አንቀጹ ቀጥሎ አራት ነጥብ ያስፈልገዋል ።

ም·16 የተወለድኩት አዲስ አበባ ነው ።

ም·17 መጻሕፍቱን ያዝና ወደ ቤታችን እንሒድ ።

### 7·5 የቃለ አጋኖ ምልክት (ትእምርተ አንክሮ)!

የቃለ አጋኖ ምልክት የመደሰትን ፡ የመቆጣትን ፡ የመቆጨትን የመገረምንና የመሳሰለውን ኃይለኛ ስሜት ከሚገልጽ ቃል ፡ ሐረግ ወይንም ዐረፍተ ነገር ቀጥሎ ይገባል።

ም.18 እሰይ ! ሙሉጌታ ወልደየስ ግሩም ግብ አገባ !

ም.19 አንት እርጉም ! ከፊቴ ጥፋ !

ም.20 ወይኔ ! እኔ ኖሬ ቢሆን ኖሮ !

ም.21 እንዴት ያለ ሾሌ ነው በል !

### 7.6 የጥያቄ ምልክት (?)

7.6.1 በመጠይቅ ቃሚት አማካኝነት ጥያቄ ሲቀርብ በዐረፍተ ነገሩ መጨረሻ የጥያቄ ምልክት ይደረጋል ።

ም.22 ወንድምህ መቼ መጣ ?

ም.23 ወዴት መሔድህ ነው ?

ም.24 ምን ልትገዛ ነው ?

ም.25 የሚመጣው እንግዳ ማን ነው ?

ም.26 ነገ ትመጣለህ ወይ ?

ም.27 መጽሐፉን አነበብከውን ?

7.6.2 የጥያቄ ቃል ባይኖርም ፡ የማንኛውም ዐረፍተ ነገር ማሰሪያ አንቀጽ ከፍ ባለ ድምፅ ከተነገረ ዐረፍተ ነገሩ የጥያቄ ምልክት ይደረግበታል ። እንዲህ ያለው ዐረፍተ ነገር ሐሳብ ሳይደመ ደም ተንጠልጥሎ መቅረቱን ያሳያል ።

ም.28 ዳሱ ተጣለ ?

ም.29 ነገ ትመጫለሽ ? ወዘተ...

7.7 ትእምርተ ጥቅስ (የጥቅስ ምልክት) /“ ”/

7.7.1 አንድ ሰው የተናገረውን ነገር ምንም ሳንለ ውጥ እንዳለ ለማመልከት ስንፈልግ በትእም ርተ ጥቅስ መካከል ለይተን እናሳያለን ። ሆኖም አብዛኛውን ጊዜ በአማርኛ ተጠቃሹን ሐሳብ የሚያመለክቱ ቃላት ወይንም ሐረጎች ስላሉ የጥቅሱ ምልክት ላያስፈልግ ይችላል ።

ም.30 የምታነበውን ነገር ተጠንቅቀህ አስተውል ሲል አስተ ማሪው መከረኝ ።

ም.31 እኔን እኮ ያስቸገረኝ ያንተ ትዕዛዝ አለማክበር ነው ካለ በኋላ ከደመወዙ 20 ብር እንዲቆረጥበት አዘዘ ።

<u>ማ ስ ታ ወ ሻ</u>

በእነዚህ ሁለት ዐረፍተ ነገሮች ላይ ትእምርተ ጥቅስ ቢደረግባቸውም ጉዳት የለውም ። ትእምርተ ጥቅስ ሲገባባቸው እንደሚከተለው ይሆናሉ ። “የምታነበ ውን ነገር ተጠንቅቀህ አስተውል” ሲል አስተማሪው

መከረኝ ። "እኔን እኮ ያስቸገረኝ ያንተ ትእዛዝ አለማክበር ነው" ካለ በኋላ ፡ ከደመወዙ 20 ብር እንዲቆረጥበት አዘዘ ።

7.7.2 የመጀመሪያው ተናጋሪ ወይንም ደራሲ የተናገረው ከየት እስከየት እንደሆን ለማወቅ በሚያጠራጥርበት ቦታ የተባለውን በትእምርተ ጥቅስ መካከል ማስቀመጥ ያስፈልጋል ።

ም.32 ከበደ ፣ ከትላንት ወዲያ "ለመምጣት ያልቻልኩት ስለ ታመምኩ ነው" አለ ።

ም.33 ከበደ "ከትላንት ወዲያ ለመምጣት ያልቻልኩት ስለታመምኩ ነው" አለ ።

7.7.3 ልዩ አጽንኦትና ትኩረት የሚገባቸው ቃላት ወይንም ሐረጎች በትእምርተ ጥቅስ ይለያሉ ።

ም.34 በአንዱ አካባቢ "አዋዜ" በሌላው "ድልህ" ይባላል ።

ም.35 "ቢሮ" በማለት ፋንታ ጽሕፈት ቤት ማለት ይሻላል ።

ም.36 አንዳንድ የገጠር ሰው "አስኳላ" ሲል ዘመናዊ ትምህርት ቤት ማለቱ ነው ።

7.8 ነጠብጣብ (...)

ጥቅስ በሚጠቀስበት ጊዜ ከመጀመሪያውም ሆነ ከመካከሉ ወይንም ከመጨረሻው ለምንፈልገው ጉዳይ የሚያገለግለንን ገልብጠን የማንሻውን ቃል ፡ ሐረግ ፡ ዐረፍተ ነገር ወይንም ሐተታ መዝለላችንን ለማሳየት ነጠብጣብ አድርገን እናልፋለን ። ይህንንም ስናደርግ በጥቅስ መካከል የተቀመጠው ነገር እርስ በርሱ የተያያዘና የሰዋስው ጉድለት የሌለበት

መሆን ይኖርበታል ።

ም.37 ተማሪው ስለ ፈረስ ስም ለማስረዳት ፊልን ከባላምባራስ ማኅተመ ሥላሴ መጽሐፍ ውስጥ "የፈረስ ስም አባ ወይንም አባት የሚለውን ቃል በማስቀደም ባንዱት ቃል ብቻ የተነገረ ቢሆንም ...ሲመረምሩት ግን ፡ የባለፈረሱን ጠባይ ሁናቴ ...አጠቃሎ የሚያሳይ ሰፊ ትርጉምና መግለጫ የያዘ ሆኖ ይገኛል" የሚለውን ለማብራራት ሞከረ ።

በዚህ ጥቅስ ውስጥ እንደምናየው ፡ በነጠብጣብ የታለፉት ሐሳቦች ለተማሪው ዓላማ የማያስፈልጉ ሲሆኑ የተጠቀሱትም ሐረጎች እርስ በርሳቸው የተዛመዱና የሰዋስው ጉድለት የሌለባቸው መሆናቸውንም እናስተውል ።

<u>መልመጃ</u>

በሚከተለው ምንባብ ውስጥ አስፈላጊ በሆነበት ቦታ ተስማሚውን የነጥብ ዐይነት አስገባ ።

አንድ ቀን ወጣቱ ሰው በማለዳ ተነሥቶ ፊቱን ታጥቦ ልብሱን ለብሶ ቁርሱን በልቶ ተቀምጦ ሳለ ድንገት በየጊዜው የሚያስበው የሕይወት ኑሮው ችግር ወደፊትም ያለው ጣጣ ሁሉ በዝቶ ለሰውነቱ በጣም ስለተሰማው ዕውቀት ከችግር ታድናለች ማለትን ብዙ ጊዜ ሰምቶ ነበርና ዕውቀትን አግኝቶ ደኅ ቶሎ ከብሮ ጌታ ለመሆንና ከችግሩ ለመዳን እየተመኘ ብዙ ጊዜ እየሰበ ያለችበትንም እየጠየቀ ቆይቶ ነበረና ያን ዕለት ተነስቶ በማለዳ እሱዋ ወደ አለችበት ቦታ መንገዱን ይዞ ሲሄድ ባልንጀሮቹ ስንፍናና ድንቁርና አግኝተውት ሰው ሆይ በጧት ተነሥተህ ወዴት ትሄዳለህ ብለው ስለጠየቁት

ሰውም ዕውቀትን አግኝቼ ከችግር ለመዳን እሻለሁ ያለችበትንም ጠይቄ አውቄአለሁ ወደዚያው እሄዳለሁ ሲል ስንፍና ለምን እሱዋን በመሻት ከንቱ ድካም ትደክማለህ አርፈህ ለኑሮህ እንደሆነ ቀላል ሥራ አታጣም ቤት እየጠራረግህ ተላላኪም ሆነህ የዕለት እንጀራህን ማግኘት ትችላለህ ዕውቀት እንዲህ በዋዛ የምትገኝ አይምሰልህ ይለዋል ።[13]

---

[13] ልዑል ራስ እምሩ ኃይለ ሥላሴ ፡ ሰውና ዕውቀት ፡ ትንሣኤ ዘጉባኤ ማተሚያ ቤት ፡ ጳጉሜን 5 ፡ 1948 ፡ ገጽ 15—16

## ማ ጠ ቃ ለ ያ

## የጸጸፍ ዋና ዋና ሥርዓት

ከሁሉ አስቀድመህ ማናቸውንም ጽሑፍ ጽፈህ ለሰው ልታቀርብ ወይንም ልትልክ ስትሻ ፥ ለማስረዳት የምትፈል ገው ነገር መኖሩን አረጋግጥ ። የምታስረዳው ፤ የምታሳም ነው፣ የምታስተባብለው ወይንም የምትገልጸው ሐሳብ ካለህ የሚቀጥለው ጥያቄህ ሐሳቤን እንዴት አድርጌ ላቅርበው የሚለው ይሆናል ። ለዚህ የሚከተሉትን ነጥቦች ማስተዋል ይጠቅማል።

1/ አንባቢህን ለይ ። የትምህርት ደረጃውንና ዝንባሌውን ፥ የዕድሜ ክልሉንና አካባቢውን ፤ የሙያውን ዐይነትና ልምዱን ፥ እንደነዚህ የመሳሰሉትን ሌሎች ጉዳዮች ጭምር ዕወቅ ፤ ወይንም በሐሳብህ ወስን ።

2/ የምትጽፍበትን ርእስ ደህና አድርገህ ተረዳና ዓላማህን ወስን ። ርእሱ በጣም ከመስፋቱ የተነሣ እጅግ ብዙ የሚያጽፍ ሊሆን ይችላል። ወይንም በጣም ጠባብ ይሆንና በጥቂት ዐረፍተ ነገሮች ብቻ የሚካተት ይሆናል ። ስለዚህ ርእሱን በደንብ ከገመገምክ በኋላ ፤ ካለህ የጊዜ ገደብና ችሎታ ወይንም ዝንባሌ አኳያ ይበልጥ ልታተኩርበት የምትፈልገውን ፍሬ ሐሳብ ምረጥ ። ይህም ሲሆን የምትጽፍበት ጉዳይ ጥሩ አድርገህ የምታውቀውና እማምት ውስጥ የማይጥልህ መሆን አለበት ።

ምንም ቁም ነገር ሳይኖር የባጥ የቆጡን መቀባጠር የሚቻለው ፣ ለቅርብ ጓደኛ ወይም ለቤተ ዘመድ በሚጻፍ የሰላምታ ደብዳቤ ውስጥ ብቻ ነው ። ለዚህም እንኳ ቢሆን ዓላማ ሊኖር ይቻላል ። የዚህ ዐይነቱ ጽሑፍ አብዛኛውን ጊዜ ዓላማው ወሬ ማውራት ስለሆነ ፣ በአመራረጥ ረገድ እምብ ዛም ጥንቃቄ ላያስፈልግ ይችል ይሆናል ። ሆኖም ወሬው ከአንባቢው የማወቅ ፍላጐት ጋር ቢገናዘብ መልካም ነው ።

3/ የመረጥኸውን ዓላማ በሚገባ ለማጉላት ወይንም መልክትህን ለአንባቢ ጥሩ አድርገህ ለማስተላለፍ እንድ ትችል ፣

ሀ/ ዐረፍተ ነገሮችህ ከሰዋስዋዊ ጉድለት ነጻ መሆና ቸውን አረጋግጥ ።

ለ/ የቃላትና የሐረጎች አመራረጥህ ካንባቢህ ችሎታ ጋር ተመጣጣኝ ፣ ለዓላማህም ተስማሚ ይሁን ።

ሐ/ ጽሑፍህ የሐሳብ ሰንሰለት እንዲኖረው ስለ ዐረ ፍተ ነገሮችህ ቅደም ተከተል በጣም ተጠንቀቅ ። እያንዳንዱም ዐረፍተ ነገር የፈለከውን ሐሳብ ለመግለጽ ብቃት ያለውና በትክክለኛ ቦታውም የገባ መሆኑን መርምር ።

መ/ በዝርዝር ሊገለጽ የሚገባውን ጉዳይ በደምሳሳው በአንዳንድ ዐረፍተ ነገር ነካክተህ አትለፍ ። (ይህንንም የሚወስነው ዓላማህ ነው) ።

ሠ/ ዋና ዋና ፍሬ ነገሮችን በአንቀጽ ከፋፍል ። እያንዳንዱም አንቀጽ መንደርደሪያ ዐረፍተ ነገር ቢኖረው ይመረጣል ።

ረ/ ሥርዓተ ነጥብንና ጥቅሙን ደኅና አድርገህ ተረዳ።

ሰ/ ድርሰትህ ወደ ተገቢ መደምደሚያ የደረሰ እንጂ፡ እንደ ዱብዳ ድንገት የተቋረጠ እንዳይሆን ተጠንቀቅ ።